# ምዕራፍ ፲

## የኢትዮጵያና የጣልያን ጉዳይ

**ከግንቦት እስከ ጥቅምት 1935 ዓ.ም**

በአራተኛው ምዕራፍ ላይ እንደተገለጸው፣ እ.ኤ.አ ግንቦት 25 ቀን 1935 ዓ.ም የሊግ ኦፍ ኔሽን ምክር ቤት፣ የኢትዮጵያና የጣልያን ጉዳይ በሽምግልና እንዲታይ ለሁለተኛ ጊዜ ባሳለፈው ውሳኔ መሠረት፣ ሲኞር ሙሶሊኒ ለዳኝነቱ ሥራ ከደንቡ ውጭ የራሱን ሁለት ጣልያኖች መሾሙን ያስታወቀው፣ ሰኔ 6 ቀን 1935 ዓ.ም ነበር። ኢትዮጵያ ግን የበኩልዋን ሁለት ሽማግሌዎች አንድ ፈረንሣዊና አንድ አሜሪካዊ መርጣ ያቀረበችው፣ በመጋቢት 16 ቀን 1935 ዓ.ም እንደነበረ ይታወሳል።

ግንቦት 25 ቀን በሊግ ኦፍ ኔሽን ምክር ቤት ስብሰባ ላይ የወልወል ግጭት ጉዳይ በሽምግልና እንዲታይ ዲክታተሩ ፋሽስት መፈለጉን ያስታወቀው፣ ወደ ኤርትራና ሱማሌ የሚልከውን የጦር ዝግጅት ለማጠናቀቅ ጊዜ ለማግኘት እንጂ፣ ዕርቅ ፈልጐ አለመሆኑን ያልተገነዘበ የመንግሥታት ማህበር አባል አልነበረም። በተለይም፣ ታላላቆቹ መንግሥታት ፈረንሣይና እንግሊዝ፣ የዱቼ ሙሶሊኒ ዓላማና ግብ ምን መሆኑን ደህና አድርገው ያውቃሉ። የፈረንሣይ ጠቅላይ ሚኒስትርና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር የነበረው ፒየር ላቫል፣ ጥር 6 ቀን 1935 ዓ.ም ከሙሶሊኒ ጋር የወዳጅነት ስምምነት ለመፈራረም ሮም በሄደ ጊዜ፣ ዱቼ ኢትዮጵያን ለመውረር ላለው ዕቅድ የምሥጢሩ ተካፋይ ከመሆኑም በላይ፣ ዲክታተሩ በሚወስደው እርምጃ፣ ፈረንሣይ እንደማትቃወመውና "ነፃ እጅ" (MAIN LIBRE) እንደሚኖረው ቃል ገብቶለታል። ቀጥሎም በሰኔ 24 እና 25 ቀን 1935 ዓ.ም የታላቋ ብሪታንያ የሊግ ኦፍ ኔሽን ጉዳይ ሚኒስትር አንቶኒ ኤደን ወደ ሮም ሄዶ፣ ከሙሶሊኒ ጋር በተነጋገረ ጊዜ፣ የዱቼ ውሳኔ ኢትዮጵያን በጦር ኃይል ይዞ ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ መሆኑን ዲክታተሩ በግልጽ ነግሮታል። በዚህ ጉዳይ የፈረንሣዩንና የእንግሊዙን አቋም ለይቶ ማየት ያስፈልጋል። ፒየር ላቫል ከሙሶሊኒ ጋር የሚመሠርተው ወዳጅነት ከማናቸውም ጉዳይ የሚበልጥበት ስለሆነ፣ ለዚህ ግብ የኢትዮጵያ ነፃነት መደምሰስ አያሳስበውም። አንቶኒ ኤደን ግን፣ ዱቼን ወዳጅ አድርጐ መያዝ፣ ለአውሮፓ ሰላምና ለሊግ ኦፍ ኔሽን ሕይወት አስፈላጊነቱን ቢያምንበትም፣ የኢትዮጵያ ነፃነት መነካት የለበትም ብሎ በሚቻለው ተሟግቷል። ይሁን እንጂ፣ የእንግሊዞች ተቃዋሚነት ሙሶሊኒን የሚያሳስበው ስላልሆነ፣ ኢትዮጵያን ለመውረር ያደረገውን ውሳኔ ይለውጣል ተብሎ ተስፋ የሚደረግበት አልሆነም። እንደዚሁም፣ ከኢትዮጵያ ጋር እሱ ራሱ ቀስቅሶ የፈጠረውን ጠብ፣ በሽምግልና ለመጨረስ እፈልጋለሁ እያለ ለመንግሥታት ማህበር የሚያደርገው ዲስኩር ሁሉ፣ ለጦርነት ዝግጅቱ ጊዜ ለማግኘት የማታለያ ዘዴ መሆኑ በይበልጥ እየታወቀ መጣ። ለዚህም አንዱ ማስረጃ፣ በግንቦት 25 ቀን ሊግ ኦፍ ኔሽን በሰጠው ውሳኔ መሠረት፣ ጣልያንና ኢትዮጵያ የመረጧቸው ሽማግሌዎች ወዲያውኑ ተገናኝተው ሥራቸውን መቀጠል ሲገባቸው፣ የሮማው መንግሥት ልዩ ልዩ ምክንያት እየፈጠረ እስከ ሰኔ ወር መጨረሻ ድረስ አግዶ አቆያቸው። ይህ ችግር የተፈጠረው በጣልያን መንግሥት በኩል መሆኑን ኢትዮጵያ በቴሌግራም ደጋግማ ለሊግ ኦፍ ኔሽን ስለአመለከተች፣ ሽማግሌዎቹ በሐምሌ ወር መጀመሪያ

ላይ ተሰብስበው ንግግራቸውን እንዲጀምሩ የፋሽስቱ መንግሥት መስማማቱን አስታወቀ።

ስብሰባው እንደ ተጀመረ፤ ሙሶሊኒ የሾማቸው ሁለቱ የጣልያን ዳኞች፤ « ... **የወልወል ጉዳይ ንግግር መደረግ ያለበት፤ ታህሣሥ 5 ቀን 1934 ዓ.ም ከሁለቱ አገሮች መካከል ግጭቱን ማን እንደጀመረው ለማወቅ እንጂ፤ ወልወል የኢትዮጵያ ወይም የጣልያን ግዛት መሆን አለመሆኑን ለይቶ ለመፍረድ አይደለም...** » የሚል አቋም ያዙ። ይህ ከፋሽስቶቹ ዳኞች የቀረበው ሐሳብ፤ ሕሊና ላለው ተመልካች እጅግ የሚያስገርም ብቻ ሳይሆን፤ እጅግም የሚያሳዝን ሆነ። የተጣለበትን ኃላፊነት በትክክል ለመፈጸም የሚፈልግ ዳኛ፤ ከሁሉ አስቀድሞ ምርምሩን ማካሄድ ያለበት፤ ይህ በሁለቱ አገሮች መካከል ግጭቱ የተፈጠረበት ወልወል የተባለው ቦታ የማን ግዛት መሆኑን ማጣራት ነው። የግዛቱ ባለቤት ኢትዮጵያ ነች? ወይስ ጣልያን ? ለዚህ ጥያቄ አስፈላጊው መልስ ከተገኘ በኋላ፤ በዚህ ወልወል በተባለው ቦታ ላይ ወሰን ጥሶ ጦር ያሰፈረው ማን እንደሆነና ግጭቱም እንዴት እንደተጀመረ ትክክለኛውን ሁኔታ ለማወቅ እንደሚቻል ለማንም ግልጽ ነው። በመሠረቱ፤ **"ወልወል" ከጣልያን ሱማሌ ወደ ኢትዮጵያ ግዛት አንድ መቶ ኪሎ ሜትር ወደ ውስጥ ዘልቆ የሚገኝ መሆኑን የፋሽስት መንግሥት የኮሎኒዎች ጉዳይ ሚኒስቴር በየጊዜው እየሳለ በሚያወጣው የጂዮግራፊ ካርታ ላይ ሲያረጋግጠው የቆየ ነበር።** አሁን ግን ጠቡ ከተፈጠረ በኋላ፤ የወልወል ግዛት ካለፉት ጥቂት ዓመታት ጀምሮ በጣልያን ይዞታ ውስጥ የሚገኝ ነው ሲል፤ የፋሽስት መንግሥት አዲስ መግለጫ አወጣ። እንግዲያውስ ! ወልወል የኢትዮጵያ ግዛት መሆኑን ካላመነበት፤ ከጥቂት ዓመታት ወዲህ በምን አኳኋን የጣልያን ይዞታ መሆን እንደቻለ፤ የፋሽስት መንግሥት ማስረዳት ነበረበት። ነገር ግን በተለመደው የዕብሪት መንፈሱ፤ ለዚህ ጥያቄ መልስ ለመስጠት አልገደድም ብሎ ዘጋ። በዚህ ሁኔታ፤ የሽምግልናው ሥራ እንዳይካሄድ ፋሽስቶቹ ዳኞች ምክንያት እየፈጠሩ በማስቸገራቸው፤ ሐምሌ 9 ቀን 1935 ዓ.ም የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ለመንግሥታት ማህበር ባስተላለፉት ቴሌግራም፤ በሁለቱ አገሮች መካከል የሚደረገው ንግግር ሊቀጥል አለመቻሉን አስታወቁ። ከዚህም ጋር አያይዘው፤ ወደ ኤርትራና ወደ ሱማሌ ድንበር የሮማ መንግሥት የሚያከማቸው የጦር ኃይል ብዛቱ እየጨመረ መሄዱንና በማህበሩ ደንብ መሠረት መርማሪ ኮሚሽን በአስቸኳይ ወደ ሥፍራው እንዲላክ በጥብቅ አሳሰቡ።

ሊግ ኦፍ ኔሽን፤ ይህን ከኢትዮጵያ የቀረበለትን አቤቱታ አድበስብሶ በማየት፤ ከሁለቱም ወገኖች የተመደቡት አራቱ ዳኞች በሊቀመንበርነት የሚመራቸውን አምስተኛ ዳኛ መርጠው፤ እስከ ነሐሴ ወር መጨረሻ ድረስ ጥናታቸውን እንዲቀጥሉና ሪፖርታቸውን እንዲያቀርቡ የሚል ውሳኔ ሰጠ። እንደተለመደው፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በኢትዮጵያ ወሰኖች ላይ በብዛት ስለሚሰፍረው የፋሽስት ጦር ምርመራ እንዲደረግ ያቀረቡትን ጥያቄ፤ ማህበሩ አንዳች መልስ ሳይሰጥ በቸልታ አለፈው። ፋሽስቶቹ ዳኞችም በዚህ በማህበሩ ውሳኔ ስለተደሰቱ፤ አምስተኛውን ዳኛ ለመምረጥ ጊዜ እንድናገኝ፤ ስብሰባችን እስከ ሐምሌ 30 ቀን ድረስ ይቋረጥ የሚል ሐሳብ አቀረቡ። ማን እምቢ ይበል? ....

## የእንግሊዝና የፈረንሣይ ሙከራ ምን ሊያፈራ ?

እ.ኤ.አ ነሐሴ 16 ቀን 1935 ዓ.ም የፈረንሣይ ጠቅላይ ሚኒስትር ፒየር ላቫልና የታላቋ ብሪታንያ የካቢኔ ሚኒስትር አንቶኒ ኤደን ፓሪስ ላይ ተገናኝተው ኢትዮጵያንና ጣልያንን ለማስታረቅ አንድ ሙከራ እንደሚያደርጉ የጋራ መግለጫ አወጡ። የመንግሥታት ማህበርም ሁለቱ የአውሮፓ ታላላቅ ሰዎች ለሚያደርጉት የሰላም ጥረት ከፍ ያለ አድናቆቱንና መልካም ምኞቱን በጋለ መንፈስ ገለጸላቸው።

የታወቁት ሁለቱ የፖለቲካ ሰዎች በሚያደርጉት ጥናት ላይ፤ የሙሶሊኒ እንደራሴ ባሮን አሎይዚ ተካፋይ እንዲሆን ያደረጉለትን ጥሪ ተቀብሎ ፓሪስ በመምጣቱ፤ ውይይቱ የሁለቱ አገሮች ብቻ መሆኑ ቀርቶ ጣልያንም በመጨመሩ፤ በፖለቲካ ታዛቢዎች ዘንድ የሦስቱ ኮሎኒያሊስቶች ስብሰባ ነው፤ የሚል አስተያየት ተሰጠው። እንደ እውነቱ ከሆነ፤ የታላላቆቹ መንግሥታት የእንግሊዝና የፈረንሣይ የበጐ ፈቃድ ዳኞች፤ ኢትዮጵያንና ጣልያንን እናስታርቃለን ብለው ሲነሡ፤ ከሁለቱ ባላጋራዎች መካከል አንዱን ለብቻ ለይተው የስብሰባቸው ተካፋይ ማድረግ አልነበረባቸውም። በዚህ አኳኋን፤ ኢትዮጵያ አታስፈልግም ብለው የዕርቁን ጉዳይ ከጣልያን ጋር ብቻ ለመወያየት ሲወስኑ፤ ገና ከመጀመሪያው የሚያደርጉት ጥረት ሁሉ የትክክለኛ ዳኝነት አሠራር አለመሆኑን ለመረዳት አያዳግትም።

በመሠረቱ፤ እንግሊዝና ፈረንሣይ ሙሶሊኒ ስለ ኢትዮጵያ ያለው ዕቅድና ያደረገው ውሳኔ ምን መሆኑን በትክክል የሚያውቁ ናቸው። ከዚህም በላይ ዱቼ፤ ኢትዮጵያ ቀኝ ግዛቱ እንድትሆን ያደረገውን ውሳኔ በምንም ምክንያት እንደማይለውጥ ደህና አድርገው የተረዱ ናቸው። በተለይም ፈረንሣዩ ፒየር ላቫል፤ ከስምንት ወራት በፊት (ጥር 1935) ሮም ሄዶ በኢትዮጵያ ጉዳይ ምን እንደዶለተና ምን ዓይነት የምሥጢር ስምምነት እንዳደረገ በሚገባ ያስታውሳል። አንቶኒ ኤደንም የዲክታተሩ ውሳኔ ምን ያህል የተቆረጠ መሆኑን ከሁለት ወራት በፊት (ሰኔ 1935) ሮም ሄዶ ከማንም በተሻለ በጆሮው ሰምቶ በዓይኑ አይቶ የተመለሰ ነው።

እንግዲህ፤ እነዚህ ሰዎች ጊዜው ከረፈደ በኋላ፤ በምን አኳኋን ? በምንስ ተአምር ? የዲክታተሩን እርምጃ የሚለውጥና ወደ ሰላም የሚያመራ ዘዴ ያገኛሉ ተብሎ ይጠበቃል ? በአውሮፓም ሆነ በሌላው ዓለም ያሉት የፖለቲካ ታዛቢዎች እንደገመቱት፤ የፒየር ላቫልና የአንቶኒ ኤደን ሽምግልና፤

1ኛ/ የሊግ ኦፍ ኔሽን ሕይወት በኢትዮጵያ ምክንያት የተዳከመ ሆኖ ወደ መፍረስ አቅጣጫ እንዳይጓዝ ፤

2ኛ/ ሙሶሊኒ በኢትዮጵያ ጉዳይ እንግሊዝንና ፈረንሣይን ተቀይሞ፤ ከሂትለር ጋር እንዳይሰለፍ፤

3ኛ/ ኢትዮጵያ በዲክታተሩ ተጠቅታ ነፃነቷ ሲገፈፍ፤ እንግሊዝና ፈረንሣይ እንዴት ዝም አሉ? ተብለው እንዳይተቹ፤

የተቻላቸውን ያህል የሰላም ጥረት አድርገዋል ለመባል ነው እንጂ፤ ሙከራቸው ውጤት እንደሚሰጥ አምነውበት አይደለም።

በዚህ በነሐሴው የሞቃት ወር በፓሪስ ከተማ ባደረጉት ስብሰባ፤ የእንግሊዝና የፈረንሣይ ኤክስፐርቶች ብዙ ጥናት ከአደረጉ በኋላ፤ ለፋሽስቱ መንግሥት የቀረበው የዕርቅ ሐሳብ፣

1ኛ/ ከሁሉ አስቀድሞ የኢትዮጵያ ነፃነት ተጠብቆ የሚኖር መሆኑ በይፋ እንዲገለጽ፣

2ኛ/ ኢትዮጵያ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል እንደመሆኗ መጠን፤ በጭለማው ዓለም ውስጥ የሚገኘውን የመንግሥቷን አስተዳደር በዘመናዊ መልክ ለማቋቋምና ከፍተኛ ለውጥ ለማድረግ የሚያስችላትን እርዳታ እንድትጠይቅ፣

3ኛ/ ኢትዮጵያ ለምታደርገው ከፍተኛ የአስተዳደር ለውጥ፤ የሚያስፈልጋትን ወጭ ሁሉ በሊግ ኦፍ ኔሽን በኩል የሚመደቡት የጣልያን፤ የእንግሊዝና የፈረንሣይ መንግሥታት ሲሆኑ፤ የለውጡን ሥራ በሙሉ ለማከናወን፤ ኃላፊነቱና ሥልጣኑ ለሙሶሊኒ መንግሥት እንዲሰጥ፣

4ኛ/ ኢትዮጵያ እስካሁን ከያዘቻቸው ግዛቶች ውስጥ፤ ለጣልያን መንግሥት የልማት ሥራ ጠቃሚዎች ናቸው የሚባሉትን እንደ ኦጋዴንና እንደ ከፋ የመሳሰሉትን አውራጃዎች በበጐ ፈቃድ እንድትለቅ፣

5ኛ/ የጣልያን መንግሥት በጠቅላላው በኢትዮጵያ ውስጥ ልዩ ልዩ የሆኑ የኢኮኖሚ ልማት ሥራዎችን በሙሉ ሥልጣን ለማካሄድ እንዲችል፤ ኢትዮጵያና ጣልያን በሚያደርጉት ስምምነት ላይ የታላቋ ብሪታንያና የፈረንሣይ መንግሥታት እማኞች ሆነው ፊርማቸውን ያኖራሉ፤ የሚል ነው።

ይህ የዕርቅ ሐሳብ በዝርዝር የተዘጋጀው በላቫል መሪነት ሲሆን፤ አንቶኒ ኤደን ሙሉ በሙሉ እንዳልተስማማበት አንዳንድ ምንጮች አስረድተዋል። ይኸውም፤ በዝርዝሩ አምስተኛው አንቀጽ ላይ፤ የሙሶሊኒ መንግሥት በኢትዮጵያ ግዛት ውስጥ ልዩ ልዩ የኢኮኖሚ ሥራዎችን በሙሉ ሥልጣን ያካሂዳል የተባለው፤ በኤደን አስተያየት ከሚገባ በላይ ሆኗል። የጣልያን የልማት ሥራዎች የሚከናወኑት በተወሰኑ ክልሎች ውስጥ መሆናቸው መገለጽ ነበረበት። እንደዚሁም ከፍ ብሎ በሦስተኛው አንቀጽ ላይ በኢትዮጵያ የሚደረገውን የአስተዳደር መሻሻል የሙሶሊኒ መንግሥት የሚያካሂደው፤ ከታላቋ ብሪታንያና ከፈረንሣይ ተወክሎ መሆኑ እንዲጠቀስ የአንቶኒ ኤደን ምኞት ነበር። ዞሮ ዞሮ ይህ የተሰናዳው የዕርቅ ሐሳብ፤ ኤደን እንደሚፈልገው እንኳንስ ተቀንሶለት፤ ላቫል ጽፎ እንዳቀረበውም ቢሆን ጌቶች ዱቼ የሚቀበሉት አልነበረም።

የፓሪሱ ስብሰባ ከመጀመሩ አምስት ቀናት በፊት፤ ነሐሴ 11 ቀን 1935 ዓ.ም ከምሽቱ በአንድ ሰዓት፤ መልዕክተኛው ለሆነው ለባሮን አሎይዚ ሙሶሊኒ የሰጠው እጅግ አስደናቂ የሆነው መምሪያ ከዚህ የሚከተለው ነበር። « ... ላቫልና ኤደን በፓሪስ በሚያደርጉት ስብሰባ ላይ የእኔ ዋና መልዕክተኛዬ በመሆን እንድትካፈል መርጬሃለሁ። የእኔን አደራ ተቀብለህ ወደ ፓሪስ የምትጓዘውም፤ እንደ ዲፕሎማት ጥሩ ተደራዳሪ፤ እንደ ጣልያን ኃይለኛ ተሟጋች፤ እንደ ፋሽስት ጀግና ድል አድራጊ እንደምትሆን፤ ትልቅ ተስፋ አድርጌ ነው። ዛሬ እኔ በአለሁበት

ሁኔታ፣ ከኢትዮጵያ ጋር ምንም ዓይነት የዕርቅ ድርድር አልፈልግም። እኔ የተሰናዳሁት የአድዋን ቂም ለመበቀልና የደረሰብንን ውርደት በድል ታሪክ ለመተካት ነው። የሚያረካኝም፣ ኢትዮጵያን እንደዚሁ በስጦታ መልክ ከምወስዳት፣ በጦርነት ድል አድርጌ ብይዛት ነው። ነገር ግን፣ የእንግሊዝና የፈረንሣይ መንግሥታት ጦርነት እንዳላደርግ የሚማፀኑኝ ከሆነ፣ እኔ በምጠይቀው ግዴታ ዓይነት ኢትዮጵያን ጠቅልዬ እንድይዝ መስማማት ይኖርባቸዋል። ይህም ማለት "ኢትዮጵያ" የሚባል አገር እንደማይኖር፣ ለንጉሥ ኃይለሥላሴም ቦታ እንደሌለ፣ አገሩም የፋሽስት ጣልያን፣ ንጉሡም ቪክቶር አማኑኤል ሳልሣዊ እንደሚሆኑ መታወቅ አለበት። ነገር ግን፣ ታላቋ ብሪታንያ እና ፈረንሣይ የግዴታ "ኢትዮጵያ" የሚባል አገር ለምልክት መኖር አለበት ብለው የሚያስቸግሩን ከሆነ፣ እኛ ወስነን በምንመድባቸው አውራጃዎች ላይ ንጉሡ መጠነኛ የውስጥ አስተዳደር ኦቶኖሚ ተሰጥቷቸው እንዲቆዩ ለማድረግ እንችላለን። ከዚህ ውጭ ግን አንቶኒ ኤደን ኢትዮጵያን መያዝ የሚቻለው በኤኮኖሚ መስክ ብቻ ነው እያለ በየጊዜው የሚያደነቁረንን የሰለቸ ሙዚቃ ከእንግዲህ ወዲህ መስማት የለብንም። ... በተጨማሪም ላቫልን ደህና አድርገህ እንድታስረዳው የምፈልገው፣ በኢትዮጵያ ላይ ለምንወስደው እርምጃ የሚያደርግልንን ድጋፍ ከቀጠለ፣ እኛ እሱ በተቸገረበት በትንንሾቹ የአውሮፓ አገሮች ጉዳይ ላይ መፍትሔውን አብረን እንደምናገኝለትና፣ በተለይም ሌት ተቀን የሚጨነቅበትን የሂትለርን የመስፋፋት ዕቀድ አብረን ለማገድ እንደምንችል እንዲገነዘብ ነው። ስለዚህም፣ ላቫል የሚጠቅመውን መወሰን አለበት... »

ፖምፔዎ አሎይዚ ይህን ሁሉ እጅግ የከበደ ትዕዛዝ ተሸክሞ ወደ ፓሪስ የአሥራ ስምንት ሰዓቶች የባቡር ጉዞ በሚያደርግበት ጊዜ፣ ያለጥርጥር ይዞት የሄደውን መምሪያ አንዱንም ሳይፈጽም፣ ይዞት ወደ ሮም እንደሚመለስ በሚገባ ተሰምቶታል። ለፓሪሱ ስብሰባ ዱቼ የሰጠው አስቸጋሪ መምሪያና፣ በተለይም እንደ ጣልያንነቱ ተሟጋች፣ እንደ ፋሽስትነቱ ድል አድራጊ መሆን አለብህ ብሎ፣ የጣለበትን ማስፈራሪያ በምንም ተአምር ለመፈጸም እንደማይችል ያውቀው ነበር። ጉዞውንም ከመጀመሩ በፊት በሁለት ልዩ ልዩ ቤተክርስቲያኖች ሄዶ፣ አምላኬ ጠብቀኝ ! ከወደቀብኝ ችግር አድነኝ ! ብሎ በሰፊው ጸልይዋል።

ነሐሴ 15 ቀን 1935 ዓ.ም ከጠዋቱ በአራት ሰዓት ባሮን አሎይዚ ፓሪስ እንደደረሰ፣ በቀጥታ ወደ ኬ ዶርሰይ (QUAI D'ORSAY) ሄዶ፣ ከፒየር ላቫል ጋር ተገናኘ። ለዚህ በማግሥቱ ለሚደረገው ስብሰባ ለወዳጁ ለሙሶሊኒ፣ ፒየር ላቫል ምን ጠቃሚ ነገር አሰናድቶ እንደጠበቀው ከመናገሩ በፊት፣ ከዱቼ የተላከውን የዛቻ መልዕክት አሎይዚ በቅድሚያ ማቅረብ አስፈላጊ ሆኖ ታየው። ይህም መልዕክት ባጭሩ፣ « ... የፈረንሣይ መንግሥት በኢትዮጵያ ጉዳይ ሙሶሊኒን የሚደግፍ ካልሆነ፣ በአውሮፓ አገሮች፣ በተለይም በፈረንሣይ ላይ እያንዣበበ የመጣውን አደጋ ብቻውን ለመመከት ኃላፊነቱን መውሰድ አለበት ... » የሚል ነበር። ሙሴ ላቫል ትልቅ ጉድ ፈላበት። ዲክታተሩን እረዳለሁ ብሎ የገባውን ቃል ለመፈጸም በተነሣ ቁጥር፣ በአንድ በኩል የፈረንሣይ ፓርላማ፣ በሌላ በኩል የእንግሊዙ ሚኒስትር አንቶኒ ኤደን ምን ያህል እየተከታተሉ የሚያስቸግሩት መሆኑን የሙሶሊኒ እንደራሴ እንዲያውቅለት በብርቱ ተማፀነ። « ... የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት የውጭ ፖሊሲ የተመሠረተው በመንግሥታት ማህበር ደንብ ላይ መሆኑን ያገሬ የፓርላማ አባሎች ስለሰሙ፣ ፈረንሣይም በተለይ በኢትዮጵያ ጉዳይ አቋሟን ከእንግሊዞች ጋር ማስተባበር ይገባታል ብለው ተነሥተውብኛል። እናንተም በብዙ ረገድ እንዳስተዋላችሁት፣ በአንቶኒ ኤደንና በእኔ መካከል ስለ ፋሽስት



ከግራ ወደ ቀኝ አንቶኒ ኤደን፣ ፒየር ላቫልና የሙሶሊኒ መልዕክተኛ ባሮን አሉይዚ፤

መንግሥት ሆነ ስለ ኢትዮጵያ የወደፊት ሁኔታ ተመሳሳይ አመለካከት የለንም። ለምሳሌ፤ በኢትዮጵያ ውስጥ የሙሶሊኒ መንግሥት አስተዳደሩን ለማሻሻልና ከፍ ያለ ለውጥ ለማድረግ፤ በተጨማሪም ቀድሞ ተስማምተንበት የነበረውን ኢኮኖሚውን በየመስኩ ለማልማት፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን የታወቀ ኃላፊነት ሊሰጠው ይገባል ብዬ ስናገር፤ ኤደን ይነሣና ተለይቶ የሚሰጠውን ግዛት ከማልማት በስተቀር ሌላ ተጨማሪ ሥልጣን መስጠት የለብንም ይላል። ከብዙ ክርክር በኋላ፤ ኢትዮጵያን ለማሠልጠን በሊግ ኦፍ ኔሽን ስም አስፈላጊውን ወጭ የሚሸፍኑት ሦስቱ መንግሥታት እንግሊዝ፤ ጣልያንና ፈረንሣይ ከሆኑ፤ ለሥራው አስፈጻሚነት ከመካከላችን ጣልያን ቢሆን ምን አለበት ? ብዬ ስጠይቀው፤ ከማቅማማት በስተቀር ለጊዜው የተቀረጠ መልስ አልሰጠኝም። እንደሚመስለኝ በበኩሌ ሰፊ ጥናት አድርጌ በአምስት አንቀጽ ከፋፍዬ ያዘጋጀሁትን ፕላን ኤደን በበኩሉ ካጠናው በኋላ፤ አስተያየቱን የሚገልጽልን ነገ ስብሰባችን በይፋ ሲጀመር ነው። አንተም በበኩልህ የእኔን ጥናት አተኩረህ በማየት መልሱን የምትሰጠኝ ነገ እንጂ ዛሬ እንዲሆን አልጠብቅም። ያዘጋጀሁት ቅን በሆነ የወዳጅነት መንፈስ ነው። አንድ ወዳጅ፤ የወዳጁ ችግር ምን መሆኑን ሊረዳለት ይገባል። ሲኞር ዱቼ ጣልያንን ከእግር እስከ ጫፍ በሙሉ ሥልጣን እንደልቡ የሚያስተዳድር መሪ ነው። እኔ በአራት መቶ የፓርላማ አባሎች ውስጥ የአንድ ድምፅ ብልጫ ለማግኘት ቀኑን ሙሉ ስደናቆር የምውል ምስኪን ጠቅላይ ሚኒስትር ነኝ። ... »

አሎይዚ ይህን የላቫልን ሮሮ በመስማት ልቡ ሳይራራ አልቀረም። ላቫል በትክክል እንዳስረዳው፤ የፋሽስቱን ዲክታተር ፍላጐት ለመፈጸም፤ ኤደን ካልተባበረው በስተቀር ብቻውን የፈለገውን ማድረግ አይችልም። ኢትዮጵያን ሠውቶ ሙሶሊኒን ለመርዳት ውስጥ ውስጡን የሚሠራው ምን እንደሆነ ከታወቀበት፤ የፓርላማው አባሎች ወዲያውኑ ግሩፕ አቋቁመው በአስቸኳይ ከሥልጣኑ እንደሚያወርዱት አይጠረጠርም። የእንግሊዙ ሚኒስትር ደግሞ እንደ ላቫል ለሙሶሊኒ መንግሥት ፍቅር ያደረበት ሰው አይደለም። ይልቁንም ፋሽስትን አጅግ የሚጠላና በግልጽ የሚቃወም ነው። በኢትዮጵያ ጉዳይ ከሁሉ አስቀድሞ የመንግሥታት ማህበር ክብር እንዳይነካ በሚቻለው ሁሉ የሚታገል ቢሆንም፤ ዲክታተሩ በጥጋብ የሚጠይቀውን ሁሉ እንደ ላቫል ተቀባይ ለመሆን የሚሞክር አይደለም። እንደሚታወሰው ኤደን፤ እስማማለሁ ብሎ ሐሳቡን ደጋግሞ የገለጸው፤ የኢትዮጵያ ነፃነት እንደተጠበቀ ሆኖ፤ የሙሶሊኒ መንግሥት በአገሪቱ ውስጥ የኢኮኖሚ ልማት የማስፋፋት ሚና እንዲኖረው ብቻ ነው። በተጨማሪም፤ ከአገሪቱ ውስጥ አንዳንዶቹ አውራጃዎች ወደ ጣልያን ግዛት እንዲዛወሩ ቢስማማም፤ የፋሽስት መንግሥት በኢትዮጵያ ላይ የፖለቲካና የአስተዳደር ሥልጣን እንዲኖረው አይፈልግም። በኤደንና በላቫል መካከል ያለው ልዩነት እዚህ ላይ ነው።

አሁን በመጨረሻ በዚህ በነሐሴ ወር 1935 ዓ.ም፤ ፒየር ላቫል ብቻውን በሰፊው አጥንቶ ያወጣው የዕርቅ ፕላን፤ ከአንቶኒ ኤደን ጋር የሚያግባባውና ፋሽስቶቹ ወዳጆቹንም የሚያስደስት ይሆናል ብሎ ብዙ ተስፋ አድርጎ ነበር። ከአምስቱ አንቀጾች ውስጥ በተለይ፤ ሙሶሊኒ በኢትዮጵያ ውስጥ የኢኮኖሚ ልማት ለማስፋፋት ከሚኖረው ሚና በላይ፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን እርዳታ አገሪቱ ለሚያስፈልጋት ጠቅላላ የአስተዳደር ለውጥ፤ ኃላፊነቱ ለፋሽስቱ መንግሥት እንዲሰጥ ላቫል ያቀረበውን ሐሳብ፤ ኤደን የሚስማማበት አልሆነም። ከዚህ በላይ ደግሞ እጅግ አስገራሚ የሆነው፤ ይህን ፕላን የእንግሊዙ ሚኒስትር ብቻ ሳይሆን፤ የዱቼ ሺፍ ደ ካቢኔ ባሮን አሎይዚም አልቀበልም ማለቱ ነው። በዚህ አኳኋን፤ በፓሪስ የተደረገው የሦስቱ ኮሎኒያሊስቶች ስብሰባ፤ ያለ አንዳች ስምምነት

መበተኑን በይፋ ከማስታወቅ በስተቀር፤ ለእነ ፒየር ላቫል ሌላ መንገድ አልነበራቸውም።

የእንግሊዝ፣ የፈረንሣይና የጣልያን መንግሥታት ባለሥልጣኖች፤ የነሐሴ ወር የበጋ ዕረፍታቸውን አቋርጠው ፓሪስ ላይ ባደረጉት ውይይት፤ ሳይግባቡና እንዳች ቁም ነገር ሳያፈሩ መለያየታቸው በፖለቲካ ታዛቢዎች ዘንድ እጅግ የሚያሳዝን ሆኖ ተገምቷል። ገና ስብሰባው ከመጀመሩ በፊት፤ የሊግ ኦፍ ኔሽን ምክር ቤት አባሎች፤ የፓሪሱ ውይይት አንድ ዓይነት ተስፋ ስለአሳደረባቸው መልካም ምኞታቸውን እንደገለጹ ይታወሳል። በዚሁ ሰሞን ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴም፤ ከአዲስ አበባ በሰጡት መግለጫ፤ « ... ኢትዮጵያ ምንም እንኳ በፓሪሱ ምክር ውስጥ እንድትካፈል ባይደረግም፤ የፈረንሣይና የእንግሊዝ መንግሥታት ጦርነትን ለማስቀረት የሚያደርጉት ድካም ሁሉ የተቃና እንዲሆንላቸው ከልባችን እየተመኘን፤ እነዚህ ሁለቱ ወዳጆቻችን የሆኑት አገሮች የሊግ ኦፍ ኔሽን መሠረታዊ አቋም የሆነውን ትክክለኛ ፍርድ እንደሚያስፈጽሙ፤ እኔና ሕዝቤ የተለየ ተስፋ እንጥልባቸዋለን ... » ብለው ነበር። የሆነ ሆኖ የፓሪሱ የሦስት መንግሥታት ስብሰባ የተጣለበትን አደራ ሳይፈጽም፤ ወይም ደግሞ ለወደፊቱ ጦርነቱን ለማቆም የሚያስችል አንድ ዓይነት የተስፋ ብልጭታ እንኳን ሳይሰጥ፤ እንዲሁ በደፈናው በመበተኑ ያላዘነና ያልተገረመ የለም።

ባሮን አሎይዚ ለሙሶሊኒ በላከው ራፖር፤ የፓሪሱ ስብሰባ ውጤት ሳይሰጥ የቀረው በአንቶኒ ኤደን አስቸጋሪነት መሆኑንና፤ ፒየር ላቫል ደግሞ ለጣልያን ያደረገውን ድጋፍ ዘርዝሮ በሰፊው ስለአስረዳ፤ ዱቼ ለፈረንሣዩ ጠቅላይ ሚኒስትር የሚከተለውን ቃል በቴሌግራም አስተላለፈ። « ... በእርስዎ በኩል የተጠናልንን ሐሳብ ዛሬ በአለንበት ሰዓት ልንቀበለው ባለመቻላችን እናዝናለን። ይህ ሐሳብ ከዛሬ ስምንት ወራት በፊት ቀርቦልን ቢሆን ኖሮ፤ አንድ ዓይነት የመስማሚያ መንገድ ይከፍትልን ነበር። ዛሬ ግን በብዙ ሺህ የሚቆጠር ወታደርና ትጥቅ ከላክንና የብዙ ሚሊያርድ ወጭ ካደረግን በኋላ፤ ውሳኔያችንን መለወጥ አንችልም። ኢትዮጵያ ግን አራት መቶ ሀምሳ ሺህ (450.000) ጦር አስታጥቃ ልትወጋን ተዘጋጅታለች። ስለዚህም፤ ሳንቀደም ቀድመን መከላከል ግዴታችን ይሆናል። ምንም እንኳ የፓሪሱ ስብሰባ ለመልካም ውጤት የታደለ ሳይሆን ቢበተንም፤ ወዳጃችን ፕሬዚዳንት ላቫል ላደረጉልን ድጋፍ ሁሉ የጋለ ምስጋናችንን እንልካለን። ወደፊትም ይኸው ትብብራችን እንደሚቀጥል ተስፋ እያደረግን፤ አቋማችን ባለፈው ጥር ወር ተነጋግረን የገነባነውን ወዳጅነት የሚከተል መሆኑን እንገልጽልዎታለን ... » እንደሚታየው፤ ይህ የሙሶሊኒ የመጨረሻው ቃል የሚያመለክተው፤ ባለፈው ጥር 7 ቀን 1935 ዓ.ም፤ ላቫል ሮም ሄዶ በኢትዮጵያ ጉዳይ ከዱቼ ጋር ያደረገውን "ነፃ እጅ " "MAIN LIBRE" የተባለውን ምሥጢራዊ ስምምነት ለማስታወስ መሆኑን ነው።

ነሐሴ 18 ቀን 1935 ዓ.ም፤ ባሮን አሎይዚ ከፓሪስ ወደ ሮም ጉዞውን ከመጀመሩ በፊት፤ ከጠዋቱ በአራት ሰዓት ወደ ጠቅላይ ሚኒስትሩ ጽሕፈት ቤት ሄዶ ይህን ከሙሶሊኒ የተላከለትን ቴሌግራም ሲሰጠው፤ ላቫል እጅግ ከመደሰቱ የተነሣ፤ መልዕክቱን ሲቀበል፤ በጣም የሚወደው የ "ዶሮ" ምሳ ተዘጋጅቶ ከሮም እንደተላከለት አድርጐ ቆጥሮታል። ላቫልና አሎይዚ ከመሰነባበታቸው በፊት ባደረጉት የግል ውይይት፤ የፓሪሱ ስብሰባቸው የከሸፈው በኤደን ጠማማነት ነው በማለት በድጋሚ አውግዘዋል። በአሎይዚ አስተያየት ላቫል ያዘጋጀውን ፕላን ኤደን ተስማምቶ ሦስቱም መልዕክተኞች ፈርመውበት ለሙሶሊኒ ቀርቦለት ቢሆን ኖሮ፤ ዱቼ ይቀበለው ነበር ይላል። ምናልባትም ሊሆን ይችላል። የጌታውን ልብ

ከአሉይዚ የተሻለ የሚያውቅ የለም። የሆነ ሆኖ፤ የፓሪሱ ዓይነት ስብሰባ እንደገና አይደገምም። በሚቀጥለው በገኔቭ በሚደረገው የሊግ ኦፍ ኔሽን ጉባኤ፤ የፋሽስቱ መንግሥት እንደ እነ ላቫል ከመሳሰሉት ወዳጆቹ ጋር በኢትዮጵያ ላይ ምን ተንኮል ጠምጥሞ ይመጣ ይሆን ? የሚያሳስበው ይኼ ነበር።

## ኢትዮጵያን ከሊግ ኦፍ ኔሽን ለማስወጣት !

### የሙሶሊኒ ክስ

ሐምሌ 9 ቀን 1935 ዓ.ም የሊግ ኦፍ ኔሽን ምክር ቤት ባደረገው ስብሰባ፤ በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል የተጀመረው ሽምግልና፤ አምስተኛ ዳኛ ተመርጦ ሥራው በነሐሴ ወር መጨረሻ ላይ እንዲጠናቀቅ መወሰኑ ይታወሳል። ለአምስተኛው ዳኛ ምርጫ የቀረቡት እጩዎች፤ የሩማንያው ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ሙሴ ቲቱሌስኮ (TITULESCO) እና የግሪኩ ሚኒስትር ሙሴ ፖሊቲስ (POLITIS) ሲሆኑ፤ ኢትዮጵያ የሩማንያው ሚኒስትር እንዲመረጥ ጠይቃ ነበር። ነገር ግን፤ ሥልጣን በግፈኛው እጅ ስለሆነና ዲክታተሩ የሚፈልገው ብቻ መፈጸም ስላለበት፤ የግሪኩ ሚኒስትር የአምስተኛውን ዳኛነት ሥራ ተረከበ። ሙሴ ፖሊቲስ ሥራውን እንደጀመረ፤ የወልወል ግጭት መነሻውም ሆነ የደረሰው አደጋ፤ በጣልያን ሕገወጥነት መሆኑን የሚያስረዳ ዳኝነት ለመስጠት አዘንብሎ ነበር። ይህም እውነት መሆኑን ባሮን አሉይዚ ስለ 1935 ዓ.ም የታሪክ ሂደት በጻፈው ማስታወሻ ገጽ 299 ላይ "ግሪኩ ከድቶናል "ብሎ ጠቅሶታል። ኋላ ግን፤ አሉይዚና ላቫል በአንድነት ሆነው ዳኛው አስተያየቱን እንዲለውጥ በማስደረጋቸው፤ ፖሊቲስ አሳዛኝ የሆነ አቋም ወሰደ።

እንደሚታወሰው ኢትዮጵያ ደጋግማ ያመለከተችው፤ ከሁሉ አስቀድሞ በሁለቱ አገሮች መካከል ጦርነት የተደረገበት "ወልወል" የተባለው ቦታ የማን ግዛት መሆኑ ተለይቶ እንዲታወቅ ነበር። ነገር ግን ሙሶሊኒ የመደባቸው ዳኞች ይህን የኢትዮጵያን ጥያቄ አንቀበልም ብለው ሲያስቸግሩ የቆዩትን፤ አምስተኛው ዳኛ ከእነሱ ጋር ሆኖ ስለተስማማ፤ በወልወል ጉዳይ ጥፋተኛው ማን መሆኑ እንዳይታወቅና በሊግ ኦፍ ኔሽንም በኩል ፍርድ እንዳይሰጥበት አደረገ። ገና ከጠዋቱ የግሪኩ ዳኛ የተመረጠው በዲክታተሩ ፍላጐት ስለሆነ፤ በዳኝነቱ ጣልያንን እንደሚረዳ የታወቀ ነበር። አንድ ጊዜ ብቻ እግር አዳልጦት ወደ ትክክለኛ ፍርድ ለመግዝ ሲሞክር ቢታይም፤ ቁም ነገሩን ለፍሬ ሳያደርስ በቶሎ ወደ ፋሽስቶቹ ተመልሷል። ከዱቼ መንግሥት የተጣለበትንም አደራ በመከተል፤ በነሐሴ 31 ቀን 1935 ዓ.ም ለሊግ ኦፍ ኔሽን ምክር ቤት ባቀረበው ራፖር፤ ወልወል ላይ ለደረሰው ግጭት ጠቡን የጫረውና በኃላፊነት የሚጠየቀው ማን መሆኑን መለየት አልተቻለም የሚል፤ ግራ የሚያጋባ አስተያየት ሰጥቶ ሚሲዮኑን የፈጸመ መሆኑን አስታወቀ። በዚህም ምክንያት፤ ኢትዮጵያ በግዛቷ ላይ በግፍ የደረሰባትን ጥቃት የሚያውቅላትና ተገቢውን ፍርድ የሚሰጣት አጣች።

መስከረም 4 ቀን 1935 ዓ.ም የመንግሥታት ማህበር ጠቅላላ ጉባኤ ሲደረግ፤ ዋናው ጸሐፊ ዮሴፍ አቬኖል ባዘጋጀው አጀንዳ ላይ፤ ስለ ጣልያንና ኢትዮጵያ ጉዳይ፤

1ኛ/ ለሽምግልናው ሥራ ሊቀመንበር የሆነው ዳኛ የግሪኩ ሚኒስትር ሙሴ ፖሊቲስ የሚያቀርበው ራፖር፤

2ኛ/ ፓሪስ ላይ ከነሐሴ 16 ቀን እስከ 18 ድረስ እንግሊዝና ፈረንሣይ ያደረጉት የዕርቅ ሙከራ ውጤት፤

3ኛ/ የፋሽስት መንግሥት ባለሙሉ ሥልጣን እንደራሴ እጅግ የተከበሩ ፖምፔዎ ባሮን አሎይዚ በታላቁ ዱቼ ስም ሆነው ስለ ኢትዮጵያ ጉዳይ ለመንግሥታት ማህበር አባሎች የሚሰጡት ከፍተኛ መግለጫ፤

በቅደም ተከተል የሚቀርብ መሆኑን ገለጸ።

የሃምሳ አምስቱ አባል መንግሥታት እንደራሴዎች የተዘጋጀውን የጉባኤ አጀንዳ ሲመለከቱ፤ ከመቶ ዘጠና የሚሆኑት መልዕክተኞች (90%) ይህ በሦስተኛው ተራ ቁጥር ላይ የተመዘገበው ጉዳይ፤ ያለ ጥርጥር ክቡር ዱቼ ኢትዮጵያን ለመውጋት ያቀደውን ክፉ ሐሳብ ወደ ሰላም ለውጨዋለሁ ለማለት ይሆናል የሚል ስሜት አደረባቸው። በእንግሊዝኛ እንደሚባለው " የማይሆን ምኞት " (WISHFUL THINKING) መሆኑን የተገነዘቡት የባሮን አሎይዚን ዲስኩር ሲያዳምጡ ነው። የዲክታተሩ ዋና መልዕክተኛ ደግሞ በበኩሉ፤ ለጉባኤው በሚያሰማው ንግግር፤ ከታላላቆቹ አገሮች ከእንግሊዝና ከመስኮብ፤ እንደዚሁም ከታናናሾቹ ከሩማንያና ከሜክሲኮ በስተቀር ሌሎቹ በሙሉ ደጋፊዎቼ ስለሚሆኑ፤ ኢትዮጵያ ከሊግ ኦፍ ኔሽን አባልነት እንድትባረር ለማስወሰን፤ የሰዓት ጊዜ እንደማይወስድበት እርግጠኛነት ተሰምቶት ነበር። ንግግሩንም ከማድረጉ በፊት፤ የመንግሥታት ማህበር እንደራሴዎች በሙሉ ሰዓቱን አክብረው እንዲገኙ ለማሳሰብ፤ የዋናው ጸሐፊ የአቬኖል ቢሮ ሠራተኞች ሲሯሯጡ እንደነበረ ታይቷል። ዝግጅቱ በዚህ መልክ የታሰበበት ስለሆነ፤ መስከረም 4 ቀን 1935 ዓ.ም በአሥር ሰዓት ተኩል እጅግ የሚጠበቀውን የሙሶሊኒን ዋና እንደራሴ ንግግር ለማዳመጥ የነበረው ሕዝብ ብዛት አዳራሹን አጨናንቆት ነበር።

ቀደም ሲል እንደተጠቀሰው፤ አብዛኛዎቹ የመንግሥታት መልዕክተኞች፤ ከሚደረገው መግለጫ በታላቁ ዱቼ ቸርነት የሚሰጠውን የሰላም ተስፋ እንሰማለን ብለው ስለሚጠብቁ፤ ባሮን አሎይዚ ዲስኩሩን ከመጀመሩ በፊት ገና ወደ መናገሪያው ስገነት ሲያመራ፤ በጭብጨባ የተገለጸለት ስሜት ወሰን የሌለው ሆነ። የሙሶሊኒ እንደራሴ በዚህ በተደረገለት የጋለ አቀባበል እየተዝናና፤ « ... ከታላቁ የፋሽስት ጣልያን መሪ ከክቡር ኮማንዳቶሬ፤ ቤኒቶ፤ አምሊካር አንድሬአ፤ ሙሶሊኒ ተልኬ፤ ዛሬ ከፊታችሁ የቆምኩት፤ አንድ ትልቅ ጉዳይ ልገልጽላችሁ ነው ... » ካለ በኋላ፤ ለታላቁ ዱቼ መልዕክት መክፈቻ ያደረገው፤ « ... እኛ የሃምሳ ስድስት መንግሥታት እንደራሴዎች፤ ከዛሬ አሥር ዓመታት በፊት፤ "ኢትዮጵያ" የምትባለዋን ፍጹም ፊውዳል በሆነ በጭለማው ዓለም ውስጥ የምትገኝ የአረመኔዎች መታጐሪያ አገር፤ በሥልጣኔ እጅግ ከተራመዱትና ሕዝባቸውን በዴሞክራሲና በነፃነት ከሚያስተዳድሩት መንግሥታት እኩል፤ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል እንድትሆን ያደረግነው ውሳኔ፤ ምን ያህል ከፍተኛ ስሕተት ላይ የጣለን መሆኑን እንድትገነዘቡት፤ ትክክለኛውን መረጃ ይገልላችሁ ቀርቢያለሁ ... » በሚል ቃል ነበር። በዚህ አነጋገር፤ የሙሶሊኒ መልዕክት ዓላማውና ግቡ፤ ኢትዮጵያን ከሊግ ኦፍ ኔሽን ለማስወጣት መሆኑ በግልጽ ስለታወቀ፤ በአብዛኛዎቹ መልዕክተኞች ገጽ ላይ የሚነበበውን የኃዘን ስሜት መሰካት የሚቻል አልነበረም።

ባሮን አሉይዚ ዲስኩሩን ከመጀመሩ በፊት፣ ከመጠን በላይ በተደረገ ጭብጨባ፣ ያ የጋለ ሙቀት የሰፈነበት የስብሰባ አዳራሽ፣ ሁለት ደቂቃዎች ባልሞሉ ጊዜያቶች ውስጥ፣ ያልታሰበ የበረዶ ውሽንፍር የወረደበት ይመስል እጅግ የቀዘቀዘ ሆነ።

የሙሶሊኒ እንደራሴ ንግግሩን በመቀጠል፣ ኢትዮጵያን ከመንግሥታት ማህበር ለማስወገድ፣ የአባል አገሮችን ሙሉ ድጋፍ አገኛለሁ ብሎ በአገሪቱ ላይ አለአግባብ ያወረዳቸው ውንጀላዎችና ወቀሳዎች በምንም ዓይነት የሚታመኑና ተቀባይ የሚያገኙ አልነበሩም። « ... ኢትዮጵያ የምትባለው አገር ከተፈጠረችበት ጊዜ ጀምሮ እስካሁን ምንም ዓይነት ስብዓዊ ሆነ ዘመናዊ ሥልጣኔ ሳታገኝ፣ በጭለማው ዓለም ውስጥ ታፍና በስቃይ የምትኖር መሆኗን ለማወቅ የሚያዳግት ነገር የለም። በዚች አገር ውስጥ፣ በወግ የተቋቋመ አስተዳዳሪ መንግሥት ስለሌለ፣ የሰው ልጅ መብት በምን አኳኋን እንደሚጠበቅ፣ ዴሞክራሲያዊ ሕይወትና ትክክለኛ ፍርድ ምንና ምን መሆናቸውን፣ ሕዝቡ የማወቅ ዕድሉ ስለተዘጋበት፣ ፍጹም በሆነው ፊውዳላዊ አገዛዝ ግፉን እየተቀበለ እንዲኖር ተፈርዶበታል። ዛሬ በአለንበት በሐያኛው ክፍለ ዘመን "ኢትዮጵያ" በሚባለው አገር፣ "ንጉሥ" ማለት እንደማንም ፍጡር ሰው ነው ተብሎ የሚቆጠር አይደለም። ንጉሥ ማለት በልዩ ተአምር እግዚአብሔር የሕዝብ ገዢ እንዲሆን መርጦ የፈጠረውና አዘጋጅቶ የሚያነግሠው ስለሆነ፣ ለሥልጣኑ ወሰን፣ ለፍርዱ ገደብ አይደረግበትም። ከዚህም የተነሣ፣ በአገሪቱ ውስጥ የአስተዳደር ሥርዓትና ሕግ፣ የሕዝብ መብትና ነፃነት ከቶ የማይታወቁ በመሆናቸው፣

- የሰው ልጅ "ባሪያ" እየተባለ በግፍ እንደ አውሬ እየታደነ፣ በገንዘብ የሚሸጥበትና የሚለወጥበት፣
- የሰው ልጅ፣ አጠፋ ! ሰረቀ ቀጠፈ ! እየተባለ እንዳይሠራ፣ እንዳይሮጥ፣ እጅግ በሚያሰቅቅ ጭካኔ፣ እጅና እግሩ የሚቆረጥበት፣ ምላሱ የሚጐረድበት፣
- የሰው ልጅ፣ ነፍስ አጥፍተሃል ተብሎ፣ ያለ አንዳች መረጃ፣ በየመንደሩ በሚገኝ የባላባት ሥልጣን የሙት በቃ የሚፈረድበት፣ የፍርዱም አፈጻጸም ለደመኛው ተሰጥቶ ከሰብዓዊ ርኅራኄ ውጭ በብዙ ተሰቃይቶ ሕይወቱ የሚያልፍበት ፣

ከኢትዮጵያ በስተቀር፣ ይህን የመሳሰለ ጉድ የሚገኝበት ሌላ ነፃ መንግሥት እንደሌለ ማረጋገጥ ይቻላል።

ንጉሥ ኃይለሥላሴ የዛሬ አሥራ ሁለት ዓመት ኢትዮጵያን የመንግሥታት ማህበር አባል ለማስደረግ ባመለከቱ ጊዜ፣ ብዙዎቹ የመንግሥታት ወኪሎች በሊግ ኦፍ ኔሽን ኮሚቴ ስብሰባ ላይ ባቀረቡት አስተያየት፣ ይህች አገር ከፊውዳሉ ሥርዓትና አመራር ለመላቀቅ ገና ያልተንቀሳቀሰች ስለሆነ፣ አንድ ዓይነት ተስፋ የሚሰጥ መሻሻል አድርጋ እስከምታሳየን ድረስ መቆየት ያስፈልጋታል ብለው ነበር። በተለይም የታላቋ ብሪታንያ መልዕክተኛ፣ ኢትዮጵያ የባሪያን ንግድ በሰፊው የምታካሂድና የኮንትሮባንድ መሣሪያዎችን ወደየግዛቶቻችን በማስራጨት ሰላም የምትነሣን ከመሆኗም በላይ፣ ምንም ዓይነት መንግሥታዊ አስተዳደር የሌላት ስለሆነች፣ እንዴት አድርጋ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል ለመሆን ብቁ ትሆናለች ? ብሎ ከፍ ያለ ተቃውሞ አቅርቦ ነበር። በዚህ ጊዜ፣ ንጉሥ ኃይለሥላሴ አገሬን እጅግ

ቢበዛ በሚቀጥሉት አምስት ዓመታት ውስጥ ከፌዶዳል አገዛዝ አውጥቼ ወደ ሕገ መንግሥት አስተዳደር አሸጋራታለሁ ብለው ቃል ስለሰጡ፤ የጣልያንና የፈረንሣይ መንግሥታት በአንድነት ሆነን፤ ኢትዮጵያ ከሊግ አፍ ኔሽን የምትጠየቀውን ሁሉ ለመፈጸም ግዴታ ገብታ፤ የአባልነቱ መብት ለጊዜው እንዲሰጣት፤ የታላቋ ብሪታንያን ተቃውሞ ለማስቀረት ቻልን።

እንግዲህ! ሁላችሁም እንደምታዩት፤ ይህ ሁሉ ከተደረገ አሥራ ሁለት ዓመታት ሆነ። ኢትዮጵያ ግን፤ የዛሬ አሥራ ሁለት ዓመታት ከነበረችበት የአንድ ሳንቲ ሜትር የወደፊት እርምጃ አላደረገችም። እንዲያውም ከነበረችበት ወደ ኋላ የሚያራምዳትን የቁልቁለት አቅጣጫ በመከተል ላይ ነች ቢባል ትክክለኛ ይሆናል። ይህች አገር እስከዛሬ ድረስ፤ በሕግ ላይ የተመሠረተና አገሪቱን በሙሉ ሥልጣን የሚመራ መንግሥት እንደሌላት፤ ለሁላችንም ግልጽ ሆኖ ይታየናል። ከዚህም የተነሣ አገሪቱን በጉሳና በሀብት ተከፋፍለው የያዟት፤ ባላባቶችና ራስ ደጃዝማቾች፤ የማንንም ትዕዛዝ የማይቀበሉ፤ የፈለጋቸውን የሚያደርጉ ስለሆኑ፤ የመላዋ ኢትዮጵያ መሪ ነኝ የሚሉት ንጉሥ ኃይለሥላሴ፤ በኢንተርናሽናል ገበታ ላይ የገቡበትን ግዴታዎች ሁሉ ለመፈጸም አልቻሉም። ለምሳሌም ያህል፤

- ከዓለም ገጽ ላይ እንዲጠፋ ብርቱ ውሳኔ የተደረገበትና እጅግ የተወገዘው የባሪያ ንግድ ሥራ በኢትዮጵያ ውስጥ እስካሁን አልተቋረጠም። በቅርቡ፤ የፈረንሣይ፤ የእንግሊዝና የጣልያን ኤክስፐርቶች ባደረጉት ጥናት፤ በኢትዮጵያ ውስጥ ከባሮች የሚገኘውን አገልግሎት በሌላ መተካት ስለማይቻል፤ ቁጥራቸው ከሁለት ሚሊዮን የማያንስ ባሮች ተብለው የተሰየሙ የሰው ልጆች፤ እስከዛሬ ድረስ ነፃነታቸውን አላገኙም። ገዥዎቻቸው የሆኑት በተለይ መሳፍንትና መኳንንት፤ የንጉሥ ተፈሪን አዋጅ አንቀበልም በማለታቸው፤ እንኳንስ ቀድሞ የተገዙትን ነፃ ለማውጣት ይቅርና ዛሬም በገንዘብም ሆነ በዕቃ፤ የሚሸጡትንና የሚለወጡትን በሕጉ መሠረት መከልከል አልተቻለም።

እኔ ይህንን የባሪያ ንግድ ጉዳይ አንሥቼ በመጠኑ ያብራራሁላችሁ፤ ኢትዮጵያ ባለችበት ሁኔታና በምትፈጽማቸው አጉል ተግባሮች፤ ለራሷ ብቻ ሳይሆን፤ ለእኛና ለመንግሥታት ማህበር ድርጅታችንም ምን ያህል "ፕሮብሌም" መሆኗን ለመገንዘብ እንድትችሉ ነው።

ከዚህ ቀደም ደጋግመን እንዳመለከትነው፤ ኢትዮጵያ የቅኝ ግዛቶቻችን በሆኑት አገሮች ላይ የምትጥልብን አደጋ በየጊዜው እየጨመረ በመሄዱ፤ በዛሬው ሰዓት አንድ ዓይነት እርምጃ መውሰድ ከምንገደድበት ደረጃ ላይ ደርሰናል። ከሕግ ውጭ የምታካሂደውን በኮንትሮባንድ የመሣሪያ ንግድ ከመቀጠሏም በላይ፤ በዜጎቻችን ላይ ድንበር እየጣሰች የምትፈጽምባቸውን የዝርፊያና የግድያ ወንጀል ማቆም አልፈለገችም። አሁን በቅርቡ ዘጠኝ ወራት ከሚሆን ጊዜ በፊት፤ በሱማሊ ግዛታችን በኩል ወሰኗን አልፋ፤ ከብዙ ዓመታት ጀምሮ ይዘነው በቆየው "ወልወል" በተባለው ቦታ፤ ሰፍረው በሚገኙት የፀጥታ ጠባቂዎቻችን ላይ ያደረሰችውን ከባድ አደጋ ሁላችሁም ታስታውሳላችሁ። ኢትዮጵያ ግን፤ ይህንን ጥፋቷን አምናበት፤ ይቅርታ በመጠየቅና ከመንግሥታችን ጋር ሰላም በመፍጠር ፋንታ፤ እሷ ራሷ ቀድማ ከሳሽ በመሆኗ በመንግሥታት ማህበር ላይ የፈጠረችው ችግር እስካሁን መፍትሔ አልተገኘለትም። ከዚህ በላይ ደግሞ ከአርባ ዓመታት በፊት "ምኒልክ" የተባሉት የቀድሞ ንጉሠ ነገሥቷ አድዋ በሚባል ቦታ አድርገውት ነበር እየተባለ እንደሚነገረው፤ ፋሽስቷን ጣልያን አዋርጄ ዝና አገኝበታለሁ እያለች፤ ከአራት መቶ

ሺህ በላይ የሆነ ጦር በድንበራችን ላይ አዘጋጅታ ልትወጋን የሚያመቻትን ጊዜ ትጠባበቃለች፡፡

## የተከበራችሁ የመንግሥታት ማህበር እንደራሴዎችና ጓደኞቼ፤

እንደ ጣልያን የመሰለ እጅግ በሥልጣኔ የተራመደና የሊግ ኦፍ ኔሽን ዋና ተገን የሆነ ዴሞክራት መንግሥት፤ በምን አኳኋን፤ አረመኔና የአውሮፓውያን ጠላት ከሆነችው ከኢትዮጵያ ጋር፤ በአንድ ገበታ ላይ እኩል ማህበርተኛ ሆኖ የአባልነት ተግባሩን መቀጠል ይችላል ? ... እንዴትስ አድርጐ ኢትዮጵያ የምታደርስበትን ጥቃት እየተቀበለ ለስንት ጊዜ በትእግሥት መቆየት ይኖርበታል ? ... እጅግ የተከበረው የመንግሥታት ማህበር ድርጅታችንስ፤ ይህችን ከሥልጣኔ ርቃ በፊዎዳሉ ዓለም ውስጥ የምትዋኘውን አገር አባል አድርጐ ማቆየት ምን ጥቅም ይሰጠዋል ? ... **በእኛ በኩል ታላቁ የፋሽስት መሪያችን፤ ከእንግዲህ ወዲህ በሊግ ኦፍ ኔሽን በሚደረጉት ስብሰባዎች ላይ፤ ጣልያን ከኢትዮጵያ ጋር እኩል ወንበር ይዛ የአባልነት ተግባሯን መቀጠል እንደሌለባት አስጠንቅቀዋል፡፡** ... » ካለ በኋላ፤ ባሮን አሉይዚ በስብሰባው አዳራሽ ሰገነት ላይ ፋሽስታዊ በሆነው የማዕረግ ልብሱ አጊጦ፤ እንደ ጌታው እንደ ሙሶሊኒ ለመምሰል በአነጋገር እየተቁነጠነጠ፤ « ... **ሊግ ኦፍ ኔሽን የዓለም ሰላም ጠባቂ እንዲሆን የተጣለበትን ተስፋ በትክክል ለመፈጸም እንዲችል፤ አስፈላጊውን ሁሉ ማድረግ፤ ኃላፊነቱ የየመንግሥታቱ እንደራሴዎች መሆኑ ከታመነበት፤ ለድርጅታችን ከፋሽስታዊት ዴሞክራት ጣልያንና ከአረመኔይቱ ፊዎዳል ኢትዮጵያ የትኛዋ እንደምትጠቅም መርጦ ለመወሰን፤ ያለው ጊዜ ዛሬ ብቻ ነው** ... » በሚል ማስፈራሪያ ንግግሩን ፈጸመ፡፡

ባሮን አሉይዚ ይህን የፋከራ ዲስኩሩን ሲፈጽም፤ ንግግሩን ከመጀመሩ በፊት እንደተደረገለት ዓይነት፤ ከፍ ያለ ጭብጨባ የሚያገኝ መስሎት በየአቅጣጫው ከአንገቱ ዝቅ እያለ እጅ ሲነሣ፤ ከሦስቱ ፕሮ-ፋሽስት ከሆኑት አገሮች፤ ከኦስትሪያ፤ ከሐንጋሪያና ከአልባኒያ በስተቀር ሌሎቹ በሙሉ ፀጥ አሉበት፡፡ በተጨማሪም፤ በአብዛኞዎቹ የመንግሥታት እንደራሴዎች ገጽ ላይ የሚታየው የቅሬታና የኃዘን ስሜት፤ አሉይዚ የሚጠብቀው አልነበረም፡፡ ይህንንም እሱ ራሱ በጻፈው የግል ማስታወሻው ላይ « ... **በሊግ ኦፍ ኔሽን ማህበርተኞች ውስጥ ይህን ያህል የፋሽስት ተቃዋሚዎች መኖራቸውን አላውቅም ነበር፡፡ ሆኖም በመጨረሻው ድሉ የእኔ እንደሚሆን፤ እርግጠኛ ነበርኩ** ... » ብሏል፡፡ ምን ዓይነት ድል ? ያው ኢትዮጵያን ከማህበሩ ለማስወገድ እንጂ፤ ሌላ ምን ሊሆን ይችላል ?

ከአሉይዚ ንግግር በኋላ፤ "ስለ ኢትዮጵያ ጉዳይ **ከጣልያን መንግሥት የተዘጋጀ በሚል ርዕስ፤** (MEMOIRE DU GOUVERNEMENT ITALIEN) **በሊግ ኦፍ ኔሽን ሴክሬታሪያ ዶክመንት፤ በቁጥር** C — 340 M 171 — 193 4 SEPTEMBER 1935 **ተመዝግቦ ለእያንዳንዱ መልዕክተኛ እንዲታደል ተደረገ፡፡"** ይህ በአንድ መቶ ገጽ በፈረንሣዊኛና በእንግሊዝ ቋንቋዎች ተጽፎ ከብዙ የፊጠራ ፎቶግራፎች ጋር ታትሞ የቀረበው ዶክመንት፤ የሙሶሊኒ እንደራሴ ባደረገው ዲስኩር ውስጥ ኢትዮጵያን በመዝለፍ የገለጻቸውን ዋና ዋና ነጥቦች እየተነተነ በይበልጥ ለማብራራት የተዘጋጀ ከመሆኑ በስተቀር፤ አዲስ ነገር አልነበረውም፡፡ ይሁን እንጂ የአሉይዚ ዋና ዓላማ፤ ኢትዮጵያን ከሊግ ኦፍ ኔሽን ለማስወጣት የገለጻቸው ዋና ዋና ነቀፌታዎች በዝርዝር ተጽፈው ሲቀርቡ፤ የመንግሥታት እንደራሴዎችን የበለጠ ሊያረካቸውና

ሊያሳምናቸው ይችላል የሚል ስለሆነ፤ ከፕሮፓጋንዳው ዶክመንት የሚፈልገውን ውጤት እንደሚያገኝ ያሳደረው ተስፋ ከፍ ያለ ነበር።

በዚህ ጉዳይ፤ ከሁሉ ይበልጥ የፖለቲካ ታዛቢዎችን እጅግ ያሳዘናቸውና ያስገረማቸው፤ በአንድ አባል በሆነ መንግሥት ላይ፤ ሌላው አባል መንግሥት የሚነዛውን የስድብና የፕሮፓጋንዳ ጽሑፍ፤ ከሕግ ውጭ በሊግ ኦፍ ኔሽን ዶክመንት ተመዝግቦ፤ ለየአገሩ መልክተኞች ሲሰራጭ መታየቱ ነው። የፋሽስት መንግሥት ልዩ ወዳጅ የሆነው የሊጉ ዋና ጸሐፊ ዮሴፍ አቬኖል፤ በሊጉ ስም በኢትዮጵያ ላይ የሚፈጽመው ሕገ ወጥ ሥራ፤ በዚህ በሱ ቢሮ ተቀነባብሮ በተሰራጨው የፕሮፓጋንዳ ዶክመንት ብቻ የተወሰነ አልነበረም። እንደ እነ ሔንሪ ደ ሞንፍሬይድ (HENRY DE MONFREID) የመሳሰሉት ሐቀኝነት የሌላቸው ልዩ ልዩ የውጭ አገር ደራሲዎች፤ ስለ ኢትዮጵያ አስተዳደር ከሚገባ በላይ እየነቀፉ የጻፏቸውን መጻሕፍቶች፤ ባሮን አሎይዚ እየሰበሰበ ሲልክለት ዋናው ጸሐፊ ተቀብሎ ወዲያውኑ ለየአገሩ መልዕክተኞች ያከፋፍላል። ይህን የመሰለው አሠራር፤ የማህበሩ ዋና ጸሐፊ ተግባር አለመሆኑንና፤ እስካሁንም ያደረገው ከሕግ ውጭ እንደሆነ፤ አቬኖል ሳያውቅ ቀርቶ አይደለም። ነገር ግን፤ በዚያን ሰዓት ታላላቅ የተባሉት የአውሮፓ መንግሥታት ለዱቼ ሙሶሊኒ ያላቸው ድክመትና የሚያሳዩት ትዕግሥት ከፍ ያለ ስለሆነ፤ አቬኖል ያለ ጥርጥር እኔን ማን ደፍሮ ይወቅሰኛል ? የሚል ስሜት እንዳደረበት ማመን ይቻላል። ስለዚህም፤ ከሙሶሊኒ እንደራሴ ጋር ያለው ቅርበትና ወዳጅነት እጅግ የጋለ መሆኑ በግልጽ ይታይ ነበር። አሎይዚ በራሱ የታሪክ ማስታወሻው ላይ እንደጻፈው፤ ለፕሮፓጋንዳው ዶክመንት ዝግጅት፤ ፒየር ላቫልና ዮሴፍ አቬኖል ምን ያህል እንደረዱትና እንዳበረታቱት ተናግሯል። በመስከረም 4 ቀን፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን ጉባኤ ላይ፤ ባሮን አሎይዚ የፕሮፓጋንዳውን ዲስኩር ተናግሮ ሲጨርስ፤ ወዳጁ ላቫል በተለይ በገለጸለት አስተያየት፤ « ... በመልዕክተኞቹ ዘንድ የጋለ ጭብጨባ ባይደረግልህም፤ እንኳንስ ሌሎቹ እንግሊዞችም ጭምር በጣም ያደነቁት ስለሆነ ውጤቱን በትዕግሥት መጠበቅ ነው... » ሲል የሰጠውን ምክር ከምስጋና ጋር አስታውሷል።*

ከአሎይዚ ዲስኩር በኋላ፤ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ዋና መልዕክተኛ ፊታውራሪ ተክለሐዋርያት መልስ ለመስጠት መብታቸውን በጠየቁ ጊዜ፤ የጉባኤው ሊቀመንበር፤ ጊዜው ስለመሸ በማግሥቱ መስከረም 5 ቀን ጠዋት የመጀመሪያው ተናጋሪ እንደሚሆኑ አስረድቶ ስብሰባውን በተነ። በዚህ ውሳኔ አሎይዚ በጣም ሲደሰት፤ ተክለሐዋርያት ቅር የተሰኙ መሆናቸውን አልደበቁም። አሎይዚ የተደሰተው፤ ኢትዮጵያ መልስ ከመስጠቷ በፊት፤ የየመንግሥታቱ እንደራሴዎች ከጣልያን የቀረበላቸውን ፕሮፓጋንዳ አንብበው በማደር፤ ጉዳዩን በሚገባ ለመረዳት ስለሚችሉ፤ ከዚህ በኋላ የሚደረገው የኢትዮጵያ ተቃውሞ ዋጋ አይኖረውም በሚል ተስፋ ነበር። በሌላ በኩል ደግሞ፤ የፋሽስት መንግሥት በኢትዮጵያ ላይ የነዛውን ዘለፋና ወቀሳ አማካሪያቸውን ፕሮፌሰር ዤዝን (Jézе) ይዘው፤ በጥንቃቄ ለማጥናትና ለተገቢው መልስ ዝግጁ ለመሆን፤ ፊታውራሪ ተክለሐዋርያት የአንድ ምሽትና ሌሊት ጊዜ ማግኘታቸው የሚከፋ አልሆነም።

---

* BARON ALOISI JOURNAL SEPT. 1935

# እናንተው ፍረዱ
## የኢትዮጵያ መልስ፣

ሐሙስ መስከረም 5 ቀን 1935 ዓ.ም ከጠዋቱ በአራት ሰዓት የጉባኤው ሊቀመንበር መስከባዊው ሊትቪኖፍ (Litvinof) ስብሰባውን ሲከፍት የሚከተለውን መግለጫ ሰጠ። « ... ትናንት ከእኩለ ቀን በኋላ በነበረን ፕሮግራም፣ ክቡር የጣልያን መልዕክተኛ ያደረጉልን ንግግር ሰፊ ከመሆኑ የተነሣ ጊዜ ስለአጠረን፣ ክቡር የኢትዮጵያ መልዕክተኛ መልስ ለመስጠት የጠየቁንን ለመቀበል አልቻልንም ነበር። ለዚህም ከፍ ያለ ይቅርታ በድጋሚ እየጠየቅን፣ ለክቡር ሚኒስትር ተክለ ሐዋርያት መድረኩን እንሰጣለን። በተጨማሪ፣ እኔ በሊቀመንበርነቴ ሁላችሁም እንድታውቁት የምፈልገው፣ የጣልያን ዋና መልዕክተኛ ክቡር ባሮን አሉይዚ፣ የኢትዮጵያ እንደራሴ ክቡር ተክለሐዋርያት በየስብሰባችን ላይ በየጊዜው በሚያደርጉት ንግግር፣ አገሬን በጣም ስለሚሰድቡና መንግሥቴን ለማዋረድ ስለሚጥሩ፣ እሳቸው ለመናገር መድረኩ በሚሰጣቸው ጊዜ፣ በወንበሬ ላይ አልገኝም ብለው አስታውቀውኛል። እንደምታውቁት ይህን የመሰለው ውሳኔ የእያንዳንዱ አባል አገር እንደራሴ መብት ስለሆነ፣ አስተያየት የምንሰጥበት ጉዳይ አይደለም። ሥራችንን በመቀጠል፣ አሁን የኢትዮጵያ መልዕክተኛ ወደ መናገሪያው ሰገነት መጥተው መግለጫቸውን እንዲሰጡ በአክብሮት እጠራቸዋለሁ። <u>ፊታውራሪ ተክለ ሐዋርያት !</u>

### ክቡር ሊቀመንበር፣

### የተከበራችሁ ጓደኞቼ፣ የመንግሥታት እንደራሴዎች፣

የፋሽስት መንግሥት ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ክቡር ባሮን አሉይዚ፣ የኢትዮጵያ መልዕክተኛ የአገሬን መንግሥት የሚጠላና የሚሳደብ ስለሆነ፣ እሱ በሚናገርበት ጊዜ ከስብሰባው አዳራሽ ወንበሬን ለቅቄ እወጣለሁ ሲል የነገረዎትን፣ የየመንግሥታቱ እንደራሴዎች እንዲያውቁት በማድረግዎ ከልብ አመሰግንዎታለሁ። እንደዚሁም በዚህ ጉዳይ ላይ ያለኝን አስተያየት ለጉባኤው እንድገልጽ ፈቃድዎን እለምናለሁ። የእኔ የመናገሪያ ተራ ሲደርስ፣ የፋሽስቱ መንግሥት ዋና መልዕክተኛ ወንበሩን ለቅቆ ከአዳራሹ ፈርጥጦ የወጣው፣ በእኔ ተሳዳቢነትና ፀረ-ፋሽስትነት ምክንያት አለመሆኑን ሁላችሁም እንድትረዱልኝ አጥብቄ እጠይቃለሁ። ከሁሉ በፊት እኔ ባለጌና ተሳዳቢ አይደለሁም። በወግና በሥርዓት አድጌ፣ የሠለጠነው ዓለም የሚጠቀምበትን በቂ ትምህርት አግኝቼ፣ ለከፍተኛ ኃላፊነት የበቃሁ ነኝ። ስለዚህ፣ ክቡር የሲኞር ሙሶሊኒ እንደራሴ፣ ዛሬ እኔ ከፊታችሁ ቀርቤ ስናገር ወንበሩን ለቅቆ የወጣው፣ በትናንትናው ዕለት በኢትዮጵያ መንግሥትና ሕዝብ ላይ ያደረገው ያ ሁሉ የብልግና ንግግርና ስድብ እጅግ አድርጐ የሚያሳፍረው መሆኑን ስለተገነዘበ ብቻ ነው።

ሁላችሁም በልማድ እንደምታውቁት፣ አንድ ጨዋ ሰው፣ ሌላውን ሰው በድሎኛል ብሎ በፍርድ ቤት ከከሰሰው በኋላ፣ ተከሳሹ መብቱ ተጠብቆ መልሱን እንዲሰጥ ሲፈቀድለት፣ ከሳሹ፣ ባለጋራዬ ሲናገር መስማት አልፈልግም ብሎ የፍርድ ቤቱን ሸንጐ ረግጦ ሲወጣ ታይቶ አይታወቅም ብዬ ስናገር፣ ተሳስተሃል የሚለኝ እንደማይኖር እርግጠኛ ነኝ። (ሳቅ በአዳራሹ) ስለዚህ፣ በትናንትናው ዕለት

የፋሽስት መንግሥት በኢትዮጵያ ላይ ያንን ሁሉ የስድብና የክስ ዲስኩር ያደረገላችሁ፤ በእውነተኛና በትክክለኛ መረጃ ላይ ተመሥርቶ ቢሆን ኖሮ፤ እኔ መልሱን ለመስጠት ከፊታችሁ ስቀርብ ሽሽቶ መውጣት አልነበረበትም። በእኛ በኢትዮጵያውያኖች ባሕልና አስተሳሰብ፤ ጨዋና ጀግና ነኝ የሚል ሰው፤ ዝናው የሚታወቅለትና የሚከበርለት፤ ለአቋሙ ፊት ለፊት ሲዋጋ፤ ለሚያምንበት ቀጥታ ሲሞግት ነው እንጂ፤ ጠቡን ጭሮ ሲሸሽ አይደለም። (ሳቅ በአዳራሹ)

የተከበራችሁ ጓደኞቼ፤

በትናንትናው ቀን ክቡር የጣልያን መልዕክተኛ ባደረገላችሁ ዲስኩርና ከሊግ ኦፍ ኔሽን ጽሕፈት ቤት ጋር በመተባበር ባቀረበላችሁ የፕሮፓጋንዳ መጽሐፍ፤ ኢትዮጵያ ምንም ዓይነት ሰብዓዊ ሥልጣኔ የሌላት የአረመኔዎች አገር ነች ሲል፤ በሰፊው ገልጾላችኋል። ባሮን አሎይዚ በአገሬ በኢትዮጵያ ላይ እስከዚህ ደፍሮ የስድብና በሐሰት ላይ የተመሠረተ የወንጀል ታሪክ ያቀረበላችሁ፤ የመንግሥታት ማህበር አባሎች የምነግራቸውን ከማዳመጥ በስተቀር፤ በመላው ዓለም ገናና ሆና በታወቀችው በፋሽስት ጣልያን ላይ እንዳች እርምጃ መውሰድ አይችሉም ብሎ እርግጠኛ በመሆን ነው፤ የሚል ስሜት አድሮብኛል። አለበለዚያ የአንድ የጨዋ መንግሥት እንደራሴ ይህን በመሰለ የብልግና አነጋገር በተከበረ የዓለም ማህበር ሸንጐ ላይ፤ ለመቅለል የሚደፍር አይመስለኝም። ያም ሆነ ይህ የመንግሥታት ማህበር እንደራሴዎች፤ የታወቀውን እውነተኛውን መሠረታዊ ታሪክ ትተው በፈጠራ የሚዘጋጀውን ፕሮፓጋንዳ ለመቀበል ጉጉት ይኖራቸዋል ተብሎ አይጠበቅም። ከሁሉ አስቀድሞ የፋሽስት መንግሥት ደህና አድርጐ እንዲረዳልኝ የምፈልገው፤ ኢትዮጵያ የአረመኔ ሕዝቦች መታጐሪያ አለመሆኗን ነው። ከጣልያን ሕዝቦች በፊት የክርስቶስን ወንጌልና የክርስትናን ዕምነት ተቀብላ ልጆቿን እያስተማረች የምትኖር አገር መሆኗን፤ የተከበረው የዓለም ታሪክ የሚያውቅላት ስለሆነ፤ በፋሽስት መንግሥት የሚነዛባት የሐሰት ፕሮፓጋንዳ፤ ክብሯን ይቀንስባታል ብዬ አልሠጋም። እኔ በበኩሌ፤ ኢትዮጵያ በታሪኳ ኩሩ ታ፤ የራስዋ በሆነው ሥልጣኔዋና ባሕሏ ተደስታ የምትኖር አገር ነች ብዬ ስናገር፤ በዘመናችን የፈለቀውን አዲሱን ሥልጣኔ ለመከተልና ከአውሮፓውያኖቹ ደረጃ ለመድረስ፤ የረዥም ዘመናት ጥረት እንደሚያስፈልጋት አልክድም። በሕዝብ አስተዳደርም ጉዳይ ሆነ በአገር ልማት፤ ከአውሮፓውያኖች ጋር ስንተያይ ብዙ ወደ ኋላ መቅረታችንንም አልደብቅም።

በጥንታዊው የግሪክ ዘመን፤ ውሸት ሳትጋለጥ ለዘለዓለሙ እንደማትኖር፤ እውነት ደግሞ ተሸፍና እንደማትቀር፤ ይነገር የነበረው ምሳሌ በአሁኑ ሰዓት ትዝ አለኝ። ስለዚህም ኢትዮጵያ አትዋሽም። እንደ አውሮፓውያኖቹ ሠልጥኛለሁ፤ ከማንም አላንስም ብላ አትሟገትም። ለመሠልጠንም ያላትን ጽኑ ፍላጐትና የምታደርገውንም ጥረት አታቋርጥም። ነገር ግን ወዳጃችን ባሮን አሎይዚ፤ በታላቁ ጌታው በሲኞር ሙሶሊኒ ስም ሆኖ ሲናገር፤ « ... ሊግ ኦፍ ኔሽን ኢትዮጵያን አባል አድርጐ ከተቀበለበት ካለፉት አሥራ ሁለት ዓመታት ወዲህ አገሪቱ የአንድ ሳንቲ ሜትር እንኳ የመሻሻል እርምጃ አላደረገችም በማለት፤ ያወረደብን ዘለፋ እጅግ የሚያስገርም ሆኖ አግኝተነዋል። ሁላችሁም እንደምታቁት፤ ዘለፋ ጨዋ የሆነ መንግሥት የሚጠቀምበት ዘዴ አይደለም። እኛም ኢትዮጵያውያን በዘለፋ ተጠቅመን የምናውቅ ባለመሆናችን፤ ከፋሽስት መንግሥት አለአግባብ ለተደረገብን ስድብና ዘለፋ የምንሰጠው መልስ በጨዋነት ላይ የተመሠረተ እንዲሆን እንፈልጋለን።

ክቡር አሉይዚ ምናልባት አልስማም ይሆናል። ወይም ሰምቶ፣ ለፕሮፓጋንዳው ጥቅም መዋሸትን መርጦ ይሆናል። ኢትዮጵያ ካለፉት አሥራ ሁለት ዓመታት ጀምሮ ብዙ ደክማለች።

- በሕገ መንግሥት ላይ የተመሠረተ አስተዳደርና በቀጥታም ባይሆን በተዘዋዋሪ ጉዳና የተመረጠ፣ (በየጊዜውም የሚመረጥ) የሕዝብ ምክር ቤት አቋቁማለች።

- የጥንታዊውን የፍርድ አመራር ለማሻሻል፣ ዘመኑ የሚጠይቀውን በአንቀጾች የተጠናቀቁ ሕግና ደንቦችን አዘጋጅታለች።

- ለነገይቷ ኢትዮጵያ ኃላፊነት የሚቀበሉ ወጣቶችን ለማሰናዳት፣ በአገር ውስጥ ዘመናዊ ትምህርት ቤቶችን በብዛት ሠርታለች። እነዚህም ትምህርት ቤቶች የሚያፈሯቸውን ወጣቶች ወደ አውሮፓና አሜሪካ እየላከች ከፍተኛ ትምህርት እንዲያገኙ ትጥራለች።

- የባሪያ ንግድ በማካሄድ የተወገዘችበትን ልማድ፣ በጠነከረ የወንጀለኛ መቅጫ ሕግ፣ የሰው ልጅ መብት እንዲጠበቅ አድርጋለች። በዛሬው ሰዓት የሰውን ልጅ "ባሪያ" እያለ ሲሸጥ ሲለውጥ የተገኘ፣ በፍርድ የሚደርስበት ቅጣት የዕድሜ ልክ እሥራት እንዲሆን ተደርጓል።

በዚህ አጋጣሚ ስለ ባሪያ ንግድ ጉዳይ በተወሰደው እርምጃ፣ የአውሮፓ ታላላቅ መንግሥታትና በተለይም የሙሶሊኒ መንግሥት ለኢትዮጵያ መሪዎች አድናቆታቸውንና ምስጋናቸውን መግለጻቸውን ማስታወስ እፈልጋለሁ። በጣልያን አገር የተቋቋመውም "የባርነት ተቃውሞ ማህበር" የኢትዮጵያ ንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱ ምኒልክና ልዑል አልጋወራሽ ተፈሪ መኰንን የዚህ ማህበር የክብር አባል እንዲሆኑ መመረጣቸውን አስታውቋል። እንደዚሁም፣ የዚህ ማህበር ፕሬዚዳንት የሆኑት ልዑል ፍራንቼስኮ ማሲሞ በጥቅምት 1928 ዓ.ም ለንጉሠ ተፈሪ መኰንን ባስተላለፉት ቴሌግራም፣ ባርነትን ለማጥፋት የኢትዮጵያ መንግሥት በወሰደው እርምጃ ያላቸውን ከፍተኛ አድናቆት ከምስጋና ጋር የገለጹ መሆናቸው መታወቅ አለበት።

እንግዲህ ! ሁላችሁም እንደምታዩት፣ ኢትዮጵያ የዛሬ አሥራ ሁለት ዓመታት የመንግሥታት ማህበር አባል በሆነች ጊዜ፣ ለድርጅቱ የሰጠችውን ቃል በሚገባ ከመፈጸም አላቋረጠችም። ይሁን እንጂ፣ ከሠለጠነው ዓለም ወደኋላ የቀረችበትን ሁሉ ለማሻሻል የምታደርገው ጥረት፣ ታላላቆቹና ባለጸጎቹ መንግሥታት የሚያስፈልጋትን እርዳታ አለመስጠታቸውን የምናገረው፣ በመረረ የኃዘን ስሜት መሆኑን እንድታውቁልኝ እፈልጋለሁ።

ኢትዮጵያ እንድትሠለጥን፣ ዘመናዊ አስተዳደር መሥርታ ልማት በማስፋፋት የሕዝቧን የኑሮ ደረጃ ለማሳደግ እንድትችል የሚፈልግ የለም። ሌላው ሁሉ ቀርቶ ነፃነቷን ይዛ መቆየቷን እንኳ የሚቃወም እንጂ፣ ከልቡ የሚደግፍ የለም ብዬ ስናገር፣ እኛ ወዳጆቿ ነን የምትሉ አንዳንዶቻችሁ መንግሥታት ቅሬታ እንደማይሰማችሁ ተስፋ አደርጋለሁ። ከዚህ በቀር ደግሞ ኢትዮጵያ ከዘመናዊው ሥልጣኔ ርቃ የተገኘችበትን ምክንያት ለማወቅ በሐቅ ላይ የተመሠረተ ምርምር ቢደረግ፣ ችግሩ ምን እንደሆነ ለመገንዘብ የሚያዳግት አልነበረም። ይኸውም፣



የሙሶሊኒ መልዕክተኛ፣ ኢትዮጵያ ከመንግሥታት ማህበር አባልነቷ መወገድ አለባት ሲል ኃጢዓቷን ዘርዝሮ አመለከተ፤



የኢትዮጵያ መልዕክተኛ በበኩላቸው "እናንተው ፍረዱ" ብለው መልስ ሰጡ፡፡

የኢትዮጵያ ትልቁ ችግሯ፣ ለነፃነቷ ሙት መሆኗ ነው። ይህንንም ነፃነት ለብዙ ሺህ ዓመታት ጠብቃ ያቆየችው፣ ነፃነቴን አጥቼ ለጠላት ተገዢ በመሆን ከምሠለጥን፣ ነፃነቴን ይዤ ከድህነቴ ጋር ብታገል ይሻለኛል ብላ ስለመረጠች ነው። የሲኞር ሙሶሊኒም ፋሽስታዊ መንግሥት ዛሬ ተነሥቶ ይህችን በነፃነቷና በታሪኳ ዳብራ የኖረች አገር፣ በጦር ኃይል ለመውረርና ተገዥው ለማድረግ ወስኖ የሚዘጋጀው፣ በአንድ በኩል በድህነቷ ምክንያት ዘመናዊ የጦር ድርጅት እንደሌላት በማወቅ ሲሆን፣ በተጨማሪ ደግሞ ትክክለኛ ፍርድ በሌለበት ዓለም ላይ፣ የፈለግኩትን ባደርግ ማን ይነካኛል ? ማንስ ይጠይቀኛል ? ብሎ እርግጠኛ በመሆን ነው።

እዚህ ላይ ጓደኞቼ የሆናችሁትን በገኔቭ የምትገኙ የዓለም መንግሥታት እንደራሴዎችን የማሳስባችሁ፣ የፋሽስት መንግሥት ዝግጅት የኢትዮጵያን ነፃነት መደምሰስ ብቻ አለመሆኑን እንድትገነዘቡልኝ ነው። በዘመናችን የደረሱት ያለፉት ታሪኮች፣ ብዙዎች ነገሮችን አስተምረውናል። ከዛሬ ሐያ ዓመታት በፊት ጥጋብ የተሰማቸው የኦስትሪያና የሐንጋሪ፣ የጀርመንና የኦቶማን ዲክታተሮች፣ የአውሮፓን ዴሞክራሲ ለማጥፋት የመጀመሪያውን የዓለም ጦርነት በከፈቱ ጊዜ፣ እነዚህን አጥፊዎች ለመደምሰስና ሰላምን ከቦታው ለመመለስ፣ በተለይ ፈረንሣይና ታላቋ ብሪታንያ፣ የብዙ ሚሊዮን ሕዝብ መሥዋዕትነት እንደጠየቃቸው ማስታወስ ያስፈልጋል። እነዚህ ዲክታተሮች ጠፍተው፣ በአውሮፓው ዓለም ሰላምና ዴሞክራሲ ሰፈነ ከተባለ በኋላ፣ የሐያ ዓመታት ዕድሜ ሳይሞላ፣ ይኸው ዛሬ እንደምናየው፣ የፋሽስት መንግሥት ተወልዶ፣ የዲክታተር ሥልጣኑን አስፋፍቶ፣ በጦር ኃይል ተደራጅቶ፣ በመጀመሪያ ኢትዮጵያን ለማጥቃትና ቀጥሎም በአውሮፓ ላይ የሰላም ጠንቅ ለመሆን እየገሰገሰ መጥቷል።

እንግዲህ የፋሽስት እንሣሥና ዝግጅት፣ ዓለምን ወደአለፈው የመከራ ዘመን እንዲዘፈቅ ለማድረግ መሆኑ በግልጽ እየታየ ዝም ተብሎ የሚጠበቅ ከሆነ፣ ከኢትዮጵያ ቀጥሎ ዕጣው የሚደርሳቸው መንግሥታት ሁሉ አደጋውን ለመቀበል መሰናዳት ይኖርባቸዋል። የነፃነታችን ጠባቂና የመብታችን አስከባሪ ይሆናል ብለን ስንተማመንበት የኖርነው የመንግሥታት ማህበር ድርጅታችንም፣ በዛሬው ሰዓት በሞትና በሕይወት መካከል ከቀረቡለት ሁለት ምርጫዎች ውስጥ አንዱን እንዲለይ የሚገደድበት ጊዜ መጥቶለታል። ይኸውም፣ የዲክታተር መንግሥት ወገን ሆኖ ጊዜያዊ የሆነ የደስታ ሕይወት እያገኘ ከመኖር፣ ወይም ደግሞ ለተመሠረተበት ዓላማ መስዋዕትነትን ተቀብሎ ለዘለዓለማዊ ሕይወቱ ዋስትና ከማግኘት፣ የትኛው እንደሚሻለው ምርጫውን በቶሎ መወሰን ይኖርበታል። ይሁን እንጂ፣ በአሁኑ ሰዓት፣ የዚህ የመንግሥታት ማህበር ድርጅታችን መሪዎች የሆኑት ሁሉ፣ ለእኛ ለድሆች አገሮች እንደሚታዩን ከሆኑ፣ ጠላት ተነሥቶ ነፃነታችንን ለመቀማት ቢወጋን፣ ከጐናችን ተሰልፈው መብታችንን ለማስከበር የሚወስዱልን አንዳች እርምጃ ይኖራል ብለን ዕምነት እንድናጣ አድርገውናል። ይህንንም ተስፋ የሚያስቆርጠውን አስተያየት ደፍሬ ለመናገር ያስቻለኝን አንዱን ምክንያት ብገልጽላችሁ፣ ምናልባት አልተሳሳተም ብላችሁ ትፈርዱልኝ ይሆናል።

በንግግሬ መቅድም ላይ እንደጠቀስኩላችሁ፣ ኢትዮጵያን ከሊግ ኦፍ ኔሽን ለማስወጣት እንድትወስኑ፣ የፋሽስት መንግሥት በትናንትናው ዕለት ያቀረበላችሁን የወንጀል መጽሐፍ፣ ሐሳብ በመስጠትም ሆነ በማዘጋጀት ከፍተኛ እርዳታ ያደረገለት፣ የማህበራችን ጽሕፈት ቤት መሪ መሆኑን በማያጠራጥር መረጃ ደርሼበታለሁ። ከዚህም በላይ እናንተም የመንግሥታት እንደራሴዎች

እንዳስተዋላችሁት፣ ይህን የፋሽስት ፕሮፓጋንዳ መጽሐፍ፣ ጉባኤው ያመረተው ዶክመንት በማስመሰል፣ በማህበራችን ዋና ጸሐፊ ሸኚ ደብዳቤ በወግ ተፈርሞ ለእያንዳንዳችሁ በኦፊሲየል እንዲደርሳችሁ ተደርጓል። እንግዲህ! ሁላችሁም በጥልቅ እንድትገነዘቡት የማሳስባችሁ፣ ይህችን የፈረደባት ኢትዮጵያን ባላጋራዋ ሆኖ ሊያጠፋት የተነሣባት የሙሶሊኒ መንግሥት፣ ብቻውን አለመሆኑንና የመንግሥታት ማህበር ጽሕፈት ቤታችንም ተባባሪው ሆኖ መገኘቱን ነው። በዓለም ላይ በመንግሥታት መካከል ሕብረትን ለመገንባትና የጋራ ፀጥታ ጠባቂ ሆኖ ዘላቂ የሆነ ሰላምን ለማጠንከር የቆመው ማህበር፣ መሠረታዊ ዓላማውን ስቶ አንዱን አባል መንግሥት ከአንዱ እየለየ እርዳታ ለመለገስ፣ ወይም ደግሞ የአንደኛው ወገን ሆኖ ሌላውን ለማጥቃት፣ የወንጀለኛው ግብረአበር ሆኖ ሲገኝ፣ ከዚህ የበለጠ የሚያሳዝን፣ ከዚህ የበለጠ የሚያሳፍር፣ ምን ጉድ ይኖራል? ብላችሁ ታስባላችሁ? ለማናቸውም፣ ዛሬ ኢትዮጵያ የምትጠይቃችሁ፣ ከፋሽስት መንግሥት በቀረበላችሁ ጥያቄ ላይ፣ ጊዜ ሳትፈጁ በቶሎ ፍርዳችሁን እንድትሰጡ ነው። ያላችሁ አማራጭ በሁለት የሚከፈል ነው። የመጀመሪያው፣ የመንግሥታት ማህበር የተመሠረተበትን ዓላማ በማክበር፣ ጉልበተኛ መንግሥት በጦር ኃይሉ ተማምኖ የደካማውን ነፃነት እንዳይደፍር፣ ለዴሞክራሲና ለትክክለኛ ፍርድ መዋጋት ነው። ሌላው ደግሞ፣ ሙሶሊኒ የኢትዮጵያን ነፃነት ቢገፍና ቅኝ ግዛቱ ቢያደርጋት፣ በአውሮፓ መንግሥታት መካከል ሰላምና ሕብረት ሊገኝ ይችላል ብላችሁ ካመናችሁ፣ ለፋሽስት መንግሥት እርዳታችሁን ማበርከት ነው። በዚህ መሠረት ከእነዚህ ከሁለቱ አማራጮች የትኛውን እንደምትወስኑ፣ ኢትዮጵያ በጉጉት ትጠብቃችኋለች። ከዚህ በተረፈ፣ እኛ እንደፋሽስት መንግሥት በባላጋራችን ላይ የወንጀል መጽሐፍ አሳትመን ለማሰራጨት የገንዘብ አቅም የለንም። የማህበራችንም ጽሕፈት ቤት ለኃይለኞቹ እንጂ፣ ለደካሞቹ መንግሥታት እርዳታ ለመስጠት ፈቃደኛ አይደለም። በዚህ ረገድ ያጋጠመንን ችግር እንድትረዱልን እየጠየቅን፣ እጅግ አስቸኳይ የሆነውን ፍርዳችሁን እንድትሰጡን አጥብቀን እንለምናለን።

ከዚህ በላይ እንደታየው፣ ፊታውራሪ ተክለሐዋርያት ለመንግሥታት ማህበር ጉባኤ ያቀረቡት አቤቱታ፣ የሙሶሊኒ ጥያቄ ምን ያህል ሕገ ወጥ መሆኑ እንዲታወቅና ለኢትዮጵያ ነፃነት መከላከያ የሆነ እርምጃ እንዲወሰድ ለማስደረግ ነበር። ነገር ግን የጉባኤው አባሎች፣ የፋሽስት መንግሥት ፋላጎት ምን መሆኑን በግልጽ የተረዱት ቢሆንም፣ የኢትዮጵያን ነፃነት ለማስከበር የሚረዳ የጠነከረ እርምጃ ለመውሰድ አልደፈሩም። እንዲሁ በደፈናው ዳር ዳሩን እያንዣበቡ፣ በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል የተፈጠረው ጠብ በሰላም ጉዳና እንዲያልቅ አጥንተው ሐሳብ የሚያቀርቡ፣ የአምስት አገሮች አባላት ያሉበት ኮሚቴ አቋቋሙ።

## የአምስቱ ኮሚቴ ጥናት

ለዚህ ሥራ የተመረጡት፣ የታላቋ ብሪታንያ፣ የፈረንሣይና የስፔን፣ የፖላንድና የቱርክ መልዕክተኞች፣ በሦስት ሳምንታት ጊዜ ውስጥ አሥራ አንድ ጊዜ ተሰብስበው ጥናታቸውን ካከናወኑ በኋላ፣ እ.ኤ.አ መስከረም 24 ቀን 1935 ዓ.ም የሚከተሉትን ሐሳቦች ለጉባኤው አቀረቡ።

ኢትዮጵያ ከመንግሥታት ማህበርና ከሌሎቹም ታላላቅ አገሮች እርዳታ እየተሰጣት፣

1ኛ/ የመንግሥቷን ጠቅላላ አስተዳደር በዘመናዊ ሥርዓት እንድታሻሽል፣

2ኛ/ ዘመናዊ የሆነ የፖሊስ ኃይል በማቋቋም፣ በግዛቶቿ ጠረፎች ላይ የሚፈጸመውን የባሪያ ንግድና በኮንትረባንድ የሚገቡትን የጦር መሣሪያዎች ገበያ እንድታስወግድ፣

3ኛ/ በአገሪቱ ውስጥ በልማድ ሲሠራባቸው የኖሩት የፍትሐ ብሔርና የወንጀለኛ መቀጫ ደንቦች ተሻሽለው እንዲወጡና፣ ዳኝነቱም የሰው ልጅ መብት በሚጠበቅበት መልክ እንዲከናወን አስፈላጊውን እንድታደርግ፣

4ኛ/ በአገሪቱ ውስጥ ጠቅላላ የኤኮኖሚ ልማት እንዲስፋፋ፣ ለታላላቆቹ የአውሮፓ አገሮች በተለይም ለጣልያን መንግሥት ሰፋ ያለ ዕድል እንድትሰጥ፣

5ኛ/ በኢትዮጵያ ውስጥ የልማት ተግባር እያከናወኑ ለሚኖሩት የውጭ አገር ዜጎች፣ ለመሥሪያ ቤታቸውና ለመኖሪያቸው ቋሚ የሆነ የፀጥታ ጥበቃ ኃይል እንድትመድብላቸው፣

6ኛ/ እነዚህን ሁሉ ዋና ዋና ጉዳዮች ለማቋቋምና በተግባር ለማዋል የመንግሥታት ማህበር የሚሾማቸውን ኃላፊዎችና ኤክስፐርቶች፣ ንጉሠ ነገሥቱ ተቀብለው የሚያስፈልጓቸውን እርዳታዎች እንዲሰጧቸው፣

7ኛ/ የእንግሊዝ መንግሥት ከዚህ ቀደም እንዳስታወቀው፣ በሱማሌላንድ ግዛቱ በኩል የሚገኘውን የዘይላን ወደብ ኢትዮጵያ እንድትጠቀምበት ለማድረግ ፈቃደኛ ስለሆነ፣ ኢትዮጵያም በበኩሏ የኦጋዴን ግዛቷን የጣልያን መንግሥት እንዲያለማው ብትለቅለት፣ በሁለቱ አገሮች መካከል የሚፈለገውን መግባባትና ሰላም ሊያዳብረው ይችላል።

በማለት፣ አምስቱ የኮሚቴ አባሎች ዝርዝር ጥናታቸውን ለዋናው ጉባኤ ባቀረቡ ጊዜ፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ወዲያውኑ የሚስማሙበት መሆኑን ሲገልጹ፣ ሲኞር ሙሶሊኒ፣ ይህን ኢትዮጵያን የሚያሻሽልና ወደፊትም ኃይሏን እየገነባች እንድታጠቃን ዕድል የሚሰጣትን ፕላን ጨርሶ እንቀበለውም ሲል አስታወቀ።

በመሠረቱ የፋሽስት መንግሥት የአምስቱ አባላት ኮሚቴ ያቀረበውን ሐሳብ መቃወሙ የሚያስደንቅ አልነበረም። ዱቼ ሙሶሊኒ በይፋ ያመለከተው፣ ኢትዮጵያ፣ ከጭለማው ዓለም ውስጥ ያልወጣች ፊዎዳል በመሆኗ፣ የመንግሥታት ማህበር ከአባልነቷ እንዲያስወጣትና የፋሽስት ቅኝ ግዛት ሆና እንድትኖር ነው እንጂ፣ ነፃነቷ ተጠብቆ ከዓለም ድርጅት እርዳታ እያገኘች እንድትሠለጥን አይደለም።

ስለ ኢትዮጵያ አስተዳደር መሻሻል፣ በአምስቱ የኮሚቴ አባሎች ተጠንቶ የቀረበውን ሐሳብ፣ የሊግ ኦፍ ኔሽን ካውንስል (ምክር ቤት) ቢደግፈውም፣ ጉዳዩ ለጠቅላላው ጉባኤ ቀርቦ እንዲፀድቅና በተግባር እንዲውል፣ ዋናው ጸሐፊ ዮሴፍ አቬኖል ተገቢውን እርምጃ ባለመውሰዱ፣ የተደረገው ጥናት እንደዚሁ በዶክመንት ላይ ተንሳፎ ቀረ። ለዚህ ጉዳይ የፋሽስቶቹ ደጋፊ ዮሴፍ አቬኖል የሰጠው ምክንያት፣ የኮሚቴውን ሐሳብ የጣልያን መንግሥት አልቀበልም በማለቱ ነው የሚል ነበር። ይሁን እንጂ፣ የፋሽስት መንግሥት "አልቀበልም" ማለት የሚችለው፣ ከኢትዮጵያ ጋር እንዲታረቅ በተለይ ኮሚቴው ያቀረበውን ሐሳብ ነው እንጂ፣

ለኢትዮጵያ አስተዳደር መሻሻል የመንግሥታት ማህበር እርዳታ እንዲሰጥ የተጠየቀውን የማገድ መብት አልነበረውም። ይህንን ጉዳይ አጥንተው ካቀረቡት ከአምስቱ የኮሚቴ አባሎች መካከል የነበረችው ፈረንሣይ፤ ተባባሪ ሆና የተገኘችውም፤ በታዛቢዎች ዘንድ የሙሶሊኒ ወገን መሆኗ እንዳይታወቅባት ለማስመሰል ሲሆን፤ ቀጥሎ ደግሞ የኢትዮጵያን አስተዳደር ለማሻሻል የተጠየቀው እርዳታ ለዋናው ጉባኤ ቀርቦ እንደማይፀድቅና እንደማይፈጸም ደህና አድርጋ ስለምታውቅ ነው። ሙሶሊኒ ባደረበት ከፍተኛ ምኞት፤ ኢትዮጵያ ከሊግ ኦፍ ኔሽን አባልነቷ ብትወገድ፤ የፋሽስት መንግሥት ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ በሚወራት ጊዜ፤ በዓለም ላይ ከደጋፊዎች በስተቀር ተቃዋሚዎች እንደማይገጥሙት እርግጠኛ እንደነበረ ይታወሳል። ይህንንም የዲክታተሩን ምኞት ለማስፈጸም፤ ወዳጆቹ የሆኑት የፈረንሣይ መንግሥት መሪ ፒየር ላቫልና የሊግ ኦፍ ኔሽን ዋና ጸሐፊ ፈረንሣዩ ዮሴፍ አቬኖል፤ በተለይ ከኦስትሪያ፣ ከሀንጋሪያና ከአልባኒያ መንግሥታት መልዕክተኞች ጋር ያደረጉት ጥረት ሊሳካላቸው አልቻለም። የሊግ ኦፍ ኔሽን ካውንስልም ምንም እንኳ የፋሽስት መንግሥት በአንድ ትልቅ ጥራዝ መጽሐፍ አሳትሞ ያቀረበለትን የወንጀል ክስ ለማዳመጥ ፈቃደኛ ሆኖ እንደነበረ ቢታይም፤ በዚህ ተመርኩዞ፤ የኢትዮጵያን የአባልነት መብት በሚመለከት ጉዳይ ለመነጋገር አልሞከረም። ሆኖም፤ የዲክታተሩን የዕብሪት ጥያቄ ባይቀበልም፤ የኢትዮጵያን ነፃነት ለማስከበር የወሰደው እርምጃ ወይም ያሳየው አቋም አልነበረም። ሊግ ኦፍ ኔሽን ደካማ በሆነውና ከአድሎ ነፃ ባልሆነ አሠራሩ፤ ለቤኒቶ ሙሶሊኒ የፈለገውን እንዲያደርግ ሜዳውን እንደለቀቀለት የሚቆጠር መሆኑን ወደፊት በምናያቸው የታሪክ ሂደቶች ልንገነዘብ እንችላለን።

Reference: a/ Societé des Nations
Journal official 1935-1936
b/ Paris: quai d'orsay
ministére des affaires e trangéses
c/ Rome : "ASMAE" Archivio diplomatico Affari ESTERI
"ACS " Archivo Centrale Dello Stato

# ምዕራፍ ፤

## ንጉሠ ነገሥቱ ክተት ሠራዊት አሉ !

### አልመሸም ወይ ?

በቀድሞው ዘመን የኢትዮጵያ ነገሥታቶች የውጭ ጠላት ሲመጣባቸው፣ ሕዝባቸውን ለማዘጋጀት "ክተት ሠራዊት" የሚል አዋጅ ያወጡ ነበር። እንደዚሁም፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ኢትዮጵያን ለመውረር በኤርትራና በሱማሌ ግዛት በኩል ተደራጅቶ የመጣባቸውን የፋሽስት ጦር ለመከላከል፣ እ.ኤ.አ መስከረም 25 ቀን 1935 ዓ.ም የክተት ሠራዊት አዋጅ ማውጣታቸውን ለመንግሥታት ማህበር አስታወቁ። በዚያን ጊዜ ንጉሠ ነገሥቱ ይህን አዋጅ ያስነገሩት፣ በየክፍለ ሀገሩና በየአውራጃው የሚገኘውን የሕዝብ ሠራዊት ለማሰባሰብና ለማዘጋጀት ነው እንጂ፣ በተሟላ የጦር ኃይል በተጠንቀቅ ከሚጠባበቀው የሙሶሊኒ ጦር ጋር ጦርነቱን ለመክፈት አልነበረም። በአውሮፓም አገሮች ሲሠራበት የቆየው ልማድ፣ አንድ መንግሥት ከሌላው ጋር ሲጋጭና ጠቡ ወደ ውጊያ እንደሚያመራ ሲታይ፣ በመጀመሪያ የሚወሰደው እርምጃ የአገሩን ጦር ለመሰብሰብና ለማዘጋጀት (Mobilisation Generale) መወሰኑን ማስታወቅ ሲሆን፣ በሁለተኛ ደረጃ ደግሞ ውጊያውን ለመጀመር ለባለጋራው የጦር መግለጫ (Declaration De Guerre) መስጠት ነው። በመሠረቱ፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴም የተከተሉት ይህንኑ ወግ ነበር። ነገር ግን፣ በዚያን ዘመን ሥልጣን የያዙት አብዛኛዎቹ የመንግሥታት ማህበር መሪዎች፣ (በተለይም የሊጉ ዋናው ጸሐፊ) የፋሽስት መንግሥት ደጋፊዎች በመሆናቸው፣ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት የአገሪቱን ነፃነት ለመግፈፍ ታጥቆ የመጣባትን ጠላት ባላት አቅም ለመከላከል እንድትችል ያወጡትን የዝግጅት አዋጅ፣ እሳቱን ለመጫር የጦር መግለጫ እንደሰጡ በማስመሰል ያሰራጩት ሰርኩለር፣ ለሙሶሊኒ የፕሮፓጋንዳ መጠቀሚያ እንዲሆን አስደረጉ። ዮሴፍ አቬኖልና ረዳቶቹ፣ የመንግሥታት ማህበር ምክር ቤት በትክክል እንዳይረዳው የሸፋፈኑት፣ ከቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የተላከው ቴሌግራም የሚከተለው እንደነበረ ለማወቅ የተቻለው፣ ከብዙ ቀናት በኋላ ነው። « ... የጣልያን መንግሥት በኤርትራና በሱማሌያ በኩል ከግማሽ ሚሊዮን በላይ የሚሆን የወታደር ሠራዊት ኃይልና ከፍተኛ የሆኑ የጦር መሣሪያዎች ጠምዶ በተጠንቀቅ ላይ ስለሚገኝ፣ እኔም በንጉሠ ነገሥትነቴ አገሬን ለመውረር የሚመጣብኝን ጠላት ለመከላከል ዝግጅት ሳላደርግ ብቀር ተግባሬን እንዳልፈጸምኩ ስለሚቆጠር፣ <u>ከዛሬ ጀምሮ ሕዝቤ ለማናቸውም አደጋ ተሰናድቶ እንዲጠብቅ የክተት ሠራዊት አዋጅ አስነግሬያለሁ።</u> የጣልያን መንግሥት በተለይ ካለፉት ዐሥር ወራት ጀምሮ ያለ ማቋረጥ በኢትዮጵያ ወሰን ላይ ይህንን ሁሉ የጦር ኃይል ሲያከማች፣ እኔ በመንግሥታት ማህበር ላይ ሙሉ ተስፋ በማድረግ አገሬ ለጦርነት እንድትዘጋጅ አላደረግኩም። ዛሬም ቢሆን የመንግሥታት ማህበር፣ ለአገሮች ነፃነትና ሰላም ያለበትን ኃላፊነትና ተግባር ይፈጽማል የሚለው ዕምነቴ የፀና ስለሆነ፣ አንዳች ምክንያት ተፈጥሮ በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል ጦርነት እንዳይነሣ፣ የፀጥታ ጠባቂዎች የሆኑት ወታደሮቼ ከኢትዮጵያ ወሰን በሠላሳ ኪሎ ሜትር ርቀት (30 Km) ወደ ውስጥ ዘልቀው እንዲጠብቁ አድርጌያለሁ። በኢትዮጵያ ወሰን ላይ የተከማቸው የጣልያን መንግሥት የጦር ኃይል ምን ያህል አሥጊ መሆኑንና የእኔም የፀጥታ ወታደሮች ሠላሳ ኪሎ ሜትር (30 Km) ርቀው እንደሚገኙ ለማረጋገጥ፣ የመንግሥታት

ማህበር በአስቸኳይ መርማሪ ኮሚሽን ልኮ እንዲረዳው በጥብቅ አሳስባለሁ። በተጨማሪም የመንግሥታት ማህበርን ጽሕፈት ቤት የምጠይቀው፤ ከዚህ ቀደም ደጋግሜ እንዳስረዳሁት፤ ኢትዮጵያ ምንጊዜም ከሰላም በስተቀር ጦርነት ፈላጊ አለመሆኗንና ለጦርነትም ምንም ዓይነት ዝግጅት የሌላት መሆኗን ለመላው አባል አገሮች እንዲገልጽልኝ ነው። .... »

እንግዲህ ! ከዚህ በላይ እንደታየው፤ መስከረም 25 ቀን 1935 ዓ.ም፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ያወጡት አዋጅ፤ ለመከላከያ ዝግጅት ለማድረግ እንጂ፤ ከሙሶሊኒ ቀድመው የጦርነቱን እሳት ለመጫር አለመሆኑ የሚያጠራጥር አይደለም። በዚህ ጉዳይ አንዳንድ የፖለቲካ ታዛቢዎች በሰጡት አስተያየት፤ በኢትዮጵያ መንግሥት በኩል የተወሰዱት እርምጃዎች ሁሉ ሐቀኝነታቸው ባያጠራጥርም፤ በፖለቲካ ጥበብ የዋህነት ያጠቃቸው ሆነው መገኘታቸውን መካድ አይቻልም ይላሉ። ትችታቸውም የሚመረኮዘው፤ በሚቀጥሉት ሁለት ዋና ዋና ጉዳዮች ላይ ነው።

አንደኛ/ ሙሶሊኒ ከሁለት ዓመታት ጀምሮ ያንን ሁሉ ጦር በኢትዮጵያ ወሰኖች ላይ ሲያከማች የቆየው፤ አገሪቱን ለመውረር መሆኑ ለማንም ግልጽ ሲሆን ንጉሠ ነገሥቱ ባላቸው አቅም ደረጃ በደረጃ መከላከያቸውን እያሰናዱ በመጠባበቅ ፋንታ፤ በመንግሥታት ማህበር ላይ ሙሉ ዕምነት ጥለው እስከ መጨረሻው ድረስ መቆየት አልነበረባቸውም።

ሁለተኛ/ ሙሶሊኒ፤ ጦርነቱን ከማፈንዳቱ ከአንድ ሳምንት በፊት፤ ጊዜው ካለቀና እንዲያውም ከመሸ በኋላ፤ የክተት ሠራዊት አዋጅ ማወጃቸውን ለሊግ ኦፍ ኔሽን በይፋ ማስታወቅ አስፈላጊ አልነበረም። ሙሶሊኒ፤ በኢትዮጵያ ወሰኖች ላይ ያንን ሁሉ የጦር ዝግጅት ሲያደርግ፤ ዓላማው ምን እንደሆነ ለመንግሥታት ማህበር በይፋ እንዳላስታወቀ መታወስ ነበረበት። ንጉሠ ነገሥቱ ለሊግ ኦፍ ኔሽንና ለዓለም መንግሥታት የሰጡት መግለጫ፤ " ኢትዮጵያ ልትወጋኝ ትዘጋጃለች " ለሚለው ለሙሶሊኒ ፕሮፓጋንዳ መጠቀሚያ ከመሆኑ በስተቀር፤ ለኢትዮጵያ ምንም ዓይነት ጥቅም አላመጣላትም።

መቸም ከውጭ ተመልካች ሆኖ አንዳንድ አስተያየት መሰንዘርና፤ ከዚያም አልፎ የጐደሉት ነገሮች እነዚህ ነበሩ እያሉ መተቸት፤ ከሁሉ የቀለለ መሆኑ የታወቀ ነው። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ፤ ሙሶሊኒ ጦሩን ከመጠን በላይ አዘጋጅቶ ኢትዮጵያን በግፍ ለመውረር ቆርጦ መነሳቱን ሳያውቁት ቀርተው አይደለም። ቀደም ሲል እንደተገለጸው፤ እስከመጨረሻው ሰዓት ድረስ ያላቸውን ጦር ሳያሰባስቡና ወደ ወሰኑ ሳያስጠጉ በትዕግሥት የጠበቁት፤ አንደኛ፤ ኢትዮጵያ አጥቂ መስላ እንዳትታይ፤ ሁለተኛ፤ ሊግ ኦፍ ኔሽን በአንድ አባል መንግሥት ላይ አደጋ ሲወድቅ በቸልታ ይመለከተዋል ብለው አለመጠርጠራቸው ነው። ይህም አቋማቸው ደግሞ ሊያስወቅሳቸው የሚገባ ነው ማለት አይቻልም።

# ክፍል ፫

# የፈረደባት ኢትዮጵያ ለሰባት ወራት

# ምዕራፍ ፩

## ሙሶሊኒ ጦርነቱ እንዲጀመር አዘዘ።

## ይድረስ ለጄኔራል ኤሚሊዮ ደ.ቦኖ !

« ... በኢትዮጵያ ላይ የምታደርገው ዘመቻ ቀድሞ እንደታሰበው ጥቅምት 5 ቀን 1935 ዓ.ም መሆኑ ቀርቶ ሁለት ቀናት አስቀድመህ ጥቅምት 3 ቀን እንድትጀምር ይሁን ... »
(የሙሶሊኒ መምሪያ)

ቤኒቶ ሙሶሊኒ፣ ካለፉት ሁለት ዓመታት ጀምሮ በኢትዮጵያ ወሰን ላይ ያከማቸው ጦር፣ አገሪቱን በአጭር ጊዜ ውስጥ ለመውረር የሚያስችለው ቢሆንም፣ ጦርነቱን ለመክፈት የዓለምን ሕዝብ በፕሮፓጋንዳ የሚያታልልበት አንድ ሰበብ መፍጠር አስፈልጐት ነበር። በዚህም መሠረት፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የመከላከያ ዝግጅት ለማድረግ መስከረም 28 ቀን 1935 ዓ.ም ለሕዝባቸው ያስነገሩት የክተት ሠራዊት አዋጅ፣ ጣልያንን ለመውጋት የገለጹት የጦር ማስታወቂያ ነው በማለት በዓለም ላይ ከፍ ያለ የፕሮፓጋንዳ ዘመቻ አደረገ። ከዚህም ጋር አያይዞ፣ በኤርትራ በኩል ለተሰለፈው የፋሽስት ጦር ዋና አዛዥ ለጄኔራል ደ.ቦኖ (De-Bono) ባስተላለፈው ትዕዛዝ፣ « ... በኢትዮጵያ ላይ የምታደርገው ዘመቻ፣ ቀድሞ እንደታሰበው ጥቅምት 5 ቀን 1935 ዓ.ም መሆኑ ቀርቶ፣ ሁለት ቀናት አስቀድመህ ጥቅምት 3 ቀን እንድትጀምር ይሁን። ... » ሲል አስታወቀው። ከዚህም ትዕዛዝ ጋር፣ « ለእርምጃህ ፈጣን፣ ለግብህ እርግጠኛ መሆን አለብህ »* የሚል ማስጠንቀቂያ አያይዞ ላከለት።

በመሠረቱ፣ ጄኔራል ኤሚሊዮ ደ.ቦኖ (Emilio De-Bono) በሚገባ የተዘጋጀ ስለነበረ፣ ጦርነቱን ቀድሞ ከተወሰነው ከሁለት ቀናት በፊት ለመጀመር ችግር አልነበረበትም። በታዘዘው መሠረት ሮብ ጥቅምት 3 ቀን 1935 ዓ.ም ከንጋቱ በአሥራ ሁለት ሰዓት የምድር ጦሩና የአየር ኃይሉ፣ የኢትዮጵያን ወሰን ጥሰው ጦርነቱን እንዲጀምሩ አደረገ። ወዲያውም፣ የፋሽስት መንግሥት፣ ከሮማ ለሊግ ኦፍ ኔሽንና ለአውሮፓ መንግሥታት መሪዎች ባስተላለፈው ቴሌግራም፣ « ... የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት በጣልያን ሕዝብ ላይ ባደረባቸው ጥላቻ መሠረት፣ እኛን ለመውጋት ያዘጋጁት ጦር ወደ ኤርትራ ግዛታችን እየተቃረበ ስለመጣብን፣ የጦር ኃይላችን የመከላከያ ውጊያ እንዲጀምር፣ በዛሬው ዕለት (ጥቅምት 3/1935) ትዕዛዝ ሰጥቻለሁ። ... » የሚል መግለጫ ላከ። ከዚህም መልዕክት ጋር በተጨማሪ በሰጠው ማብራሪያ መስከረም 28 ቀን 1935 ዓ.ም ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ ለሊግ ኦፍ ኔሽንና ለአውሮፓ መንግሥታት መሪዎች በላኩት መልዕክት፣ የኢትዮጵያ ጦር ሠራዊት ከወሰናችን ሠላሳ (30) ኪሎ ሜትር ርቆ እንዲጠባበቅ አድርጌያለሁ ብለው የተናገሩት፣ ዝግጅታቸውን ለማጠናቀቅ ጊዜ

---

* « ... It is essential to act quickly and strike surely... »



ንጉሠ ነገሥቱ "ክተት ሠራዊት" ማለት ግዴታ ሆነባቸው።

ለማግኘት ብለው ነው እንጂ፤ ጨርሶ ውሸት መሆኑን አረጋግጣለሁ ሲል አስታወቀ። መሠረት የሌለው ቅጥፈት የሚናገር የፋሽስቱ መንግሥት መሪ እንጂ፤ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት አለመሆናቸውን ከራሱ ከዲክታተሩ በስተቀር ሌላ የሚክድ አልነበረም። እሱ ራሱ እሳቱን ጭሮ ኢትዮጵያ ልትወጋኝ ወደ ግዛቴ ስለተቃረበች የመከላከያ እርምጃ ጀምሬአለሁ ብሎ የመንግሥታት ማህበርን ለማወናበድ በሞከረበት ዕለት፤ ከእኩለ ቀን በኋላ በአሥር ሰዓት፤ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ብላቴን ጌታ ኅሩይ ወልደሥላሴ፤ ለሊግ ኦፍ ኔሽን በላኩት ቴሌግራም፤ የፋሽስት የጦር ኃይል የመረብን ወሰን ጥሶ ወደ ኢትዮጵያ ግዛት መግባቱንና በትግራይ ክፍለ ሀገር አድዋንና አዲግራትን በአውሮፕላን በንብ መደብደቡን አስታውቀው ነበር።

እንደሚታወሰው፤ የወልወል ግጭት ከደረሰበት ጊዜ ጀምሮ፤ የፋሽስት መንግሥት ኢትዮጵያን በጦር ኃይል ለመውረር በኤርትራና በሱማሌ በኩል የሚያደርገው ዝግጅት እጅግ አሳሳቢ ስለሆነ፤ በደንቡ መሠረት የመንግሥታት ማህበር መርማሪ ኮሚሽን ልኮ እውነተኛውን ጉዳይ እንዲረዳው፤ ንጉሠ ነገሥቱ ከአሥር ጊዜ የበለጠ ደጋግመው ያመለከቱት የሚዘነጋ አይደለም። ነገር ግን፤ የሊግ ኦፍ ኔሽን መሪዎች ሕጉን ተከትለው ከመፈጸም ይልቅ የሙሶሊኒ ወዳጅነት ስለሚበልጥባቸው፤ የኢትዮጵያን አቤቱታ ለመስማት ሳይፈልጉ ቀሩ። በመጨረሻም ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ቢቸግራቸው፤ የተጠመደባቸውን አደጋ ለመከላከል የክተት ሠራዊት ባወጁ ጊዜ፤ የኢትዮጵያ ወታደሮች የጣልያን ግዛት ከሆነው ከኤርትራ ወሰን ሠላሳ ኪሎ ሜትር ርቀው የሚገኙ መሆናቸውን ለማረጋገጥ፤ በኢትዮጵያ መንግሥት ወጭ ሊግ ኦፍ ኔሽን መርማሪዎች ልኮ ትክክለኛውን ሁኔታ እንዲረዳው በጥብቅ አሳስበው ነበር። ይህንንም ጥያቄ ክቡር ዱቼ የማይፈቅደው ስለሆነ፤ የሊግ ኦፍ ኔሽን ዋና ጸሐፊ የኢትዮጵያን ማመልከቻ ለምክር ቤቱ ሳያቀርብ፤ ጊዜው እንዲያልፍ አደረገ። በመጨረሻው ሙሶሊኒ ያለ አንዳች መግለጫ ጦርነቱን ከከፈተ በኋላ፤ ዮሴፍ አቬኖል ምንም ለማድረግ እንደማይቻል እያወቀ፤ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት በጠየቁት መሠረት መርማሪ ኮሚሽን ለመላክ ስለሚቻልበት ጉዳይ ማጥናት ያስፈልጋል በማለት ወዲያና ወዲህ ሲሯሯጥ ታየ። በጦርነቱ እሳት ውስጥ ገብቶ ጥፋተኛውን ለመለየት ኃላፊነት የሚቀበል መርማሪ ዳኛ ከየት ነው የሚያገኘው ? ይህንን የዮሴፍ አቬኖልን ሥራ የተመለከቱ ሁሉ አጭበርባሪዎች የሚጠቀሙበት ጨዋታ መሆኑን ሳይረዱት አልቀሩም።

የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ምንም እንኳ የክተት ሠራዊት አዋጅ ያስነገሩት፤ ሙሶሊኒ ጦርነቱን ከመክፈቱ ከአምስት ቀናት በፊት ቢሆንም፤ ከአዲስ አበባ ዘማች ያሰናበቱት የፋሽስት ጦር የኢትዮጵያን ወሰን ጥሶ ወረራውን ከጀመረ ከሁለት ሳምንት በኋላ፤ ጥቅምት 18 ቀን 1935 ዓ.ም ነው። (በኢት.አቆ ጥቅምት 8 ቀን 1928 ዓ.ም) በዚያን ጊዜ የፋሽስት ጦር ትግራይ ክፍለ ሀገር ገብቶ አድዋንና አዲግራትን ይዟል።

እ.ኤ.አ ጥቅምት 18 ቀን 1935 ዓ.ም በአምስት ሰዓት፤ ንጉሠ ነገሥቱ በጃንሜዳ ተገኝተው በሰሜን በኩል የሚዘምተውን ቁጥሩ ወደ ስማንያ ሺህ የሚጠጋ ዘማች ባሰናበቱበት ጊዜ፤ የጦር ሚኒስትሩና የጦሩ አዛዥ ራስ ሙሉጌታ ይገዙ፤ « ... እኔ አሽከርህ፤ እኔ ባሪያህ ቀድሜ ሳልሞት ጠላትህ ከፊትህ አይደርስም ... » የሚል መፈክር ሲያሰሙ፤ ምናልባትም እንደ አንበሳው ምኒልክ ጊዜ የጠላት ጦር ተንኮታኩቶ ይወድቃል በሚል ተስፋ የተደረገው ጭብጨባና

የደስታ መግለጫ ጨኸት የአዲስ አበባ ከተማን አደበላልቆት ነበር። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴም በሰጡት መልስ፣ « ... ለአገርህ ነፃነትና ለኛ ለንጉሠ ነገሥትህ ክብር ደምህን ለማፍሰስ ቆርጠህ መነሣትህን በማየታችን ደስ ብሎናል። ጌታ ገንዘቡን የሚያስጠብቀው ሳመነው አሽከሩ ስለሆነ፣ አንተም እምነትህን በእግዚአብሔር ላይ አድርገህ የጦር ሠራዊታችንን እየመራህ ጠላታችንን እንድትመክት አዘንሃል ... » አሉ። ታላቁን የኢትዮጵያን ሰንደቅ ዓላማ ለጦር ሚኒስትሩ ከሰጡ በኋላ፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ለዘማቹ ሕዝብ ባደረጉት ንግግር፣ የዓለምን ሰላም ለመጠበቅ ኃላፊነት የተቀበለውን የመንግሥታት ማህበር እምነን ጦራችንን ወደ ግንባር ሳናስቀድም በመዘግየታችን፣ ጠላታችን ወሰናችንን ደፍሮ ከግዛታችን ለመግባት ችሏል። ይህም ከጥንት ጀምሮ በነፃነታችን ሲቀና የኖረው ጠላታችን፣ እንኳንስ ለወታደሮቻችን፣ ለሽማግሌና ለሴት ለሕፃናትም ጭምር የሚራራ አለመሆኑን በጦርነቱ አጀማመር አሳይቶናል። ስለዚህ፣ ሞት በሳል ሆነ በጉንፋን፣ በተስቦ በሽታ ሆነ በድንገተኛ ሕመም የሚመጣ ስለሆነ፣ ለአገር ነፃነት ከጠላት ጋር ሲዋጉ የደረሰ ሞት የጀግንነትን ክብር እጅግ የሚያጉላው መሆኑን ማወቅ ያስፈልጋል ... ካሉ በኋላ፣ « ... ዛሬ ይህንን ምክር የምንነግራችሁ ንጉሠ ነገሥታችሁ በጦርነቱ ላይ፣ በመካከላችሁ ሆነን ስለ ኢትዮጵያ ነፃነት፣ ስለተከበረው ታሪኳና ስለ ሃይማኖቷ ከእናንተው ጋር ደማችንን ለማፍሰስ የተዘጋጀን መሆናችንን ስናረጋግጥላችሁ ደስ ይለናል ... » በሚል ቃል ንግግራቸውን ፈጸሙ።

እንግዲህ ! እንደሚታየው ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ቀደም ብለው ሕዝባቸውን ለጦርነት አላዘጋጁም። ቤኒቶ ሙሶሊኒ ካለፉት ሁለት ዓመታት ጀምሮ በተለይም ከወልወል ግጭት ወዲህ ከግማሽ ሚሊዮን በላይ የሆነ የምድር ጦርና አምስት መቶ የሚሆኑ በንብ ጣይ አውሮፕላኖች በኢትዮጵያ ድንበር ዙሪያ ሲያከማች፣ ንጉሠ ነገሥቱ እምነታቸውን በሊግ ኦፍ ኔሽን ላይ ስለአሳደሩ፣ ሙሶሊኒ የማህበሩን ሕግ አፍርሶ አገሬን ለመውጋት ይደፍራል ብለው አላሰቡም። ከዚህም በላይ ነዋሪነታቸው አዲስ አበባ የሆኑት አንዳንድ የውጭ አገር መንግሥታት እንደራሴዎች በየጊዜው የሚሰጧቸው ምክር፣ « ... ለኢትዮጵያ የሚጠቅማት በምንም ምክንያት ለጦርነት የማትዘጋጅና ለሰላም የምትኖር መሆኗን ለዓለም ማሳወቅ ነው ... » የሚል ነበር። በተጨማሪም፣ « ... ኢትዮጵያ ሰላማዊነቷን በሚገባ ካሳወቀችና ካሳመነች ሙሶሊኒ ሕግ ጥሶ ጦርነት ቢያነሣባት፣ ሊግ ኦፍ ኔሽንና ታላላቆቹ መንግሥታት በተለይም ፈረንሣይና እንግሊዝ እንደሚደርሱላት የታወቀ ነው ... » እያሉ ሞራላቸውን ሲያዳብሩላቸው ቆይተዋል። ንጉሠ ነገሥቱም፣ ይህንን ምክር ያዳመጡት፣ የየመንግሥታቱ እንደራሴዎች የሚናገሩት በየመሪዎቻቸው ስም ሆነው ነው በማለት ስለሆነ፣ ዲፕሎማቶቹ ያልታዘዙትን ይናገራሉ፣ የማይሆን ነገር ፈጥረው ያወራሉ የሚል ጥርጣሬ አላደረባቸውም። በመጨረሻው ሙሶሊኒ ያለ እንዳች የጦር መግለጫ የኢትዮጵያን ወሰን ጥሶ ሲገባ፣ " ወዳጅ " የተባሉትና ዕምነት የተጣለባቸው መንግሥታት ሁሉ እንኳንስ ከጉናቸው ሊሰለፉላቸው ይቅርና የማበረታቻ ሞራል ለመስጠት እንኳ ድምፃቸውን ሲያጠፉባቸው፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ምን ያህል እንደተበሳጩ፣ ምንስ ያህል እንደአዘኑ፣ መገመት ያዳግታል። ባለንበት በዛሬው ዘመን ያለው ትውልድና ወደፊትም የሚመጣው ይህንን ታሪክ ሲመለከት፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ፈረንጆቹን ማመን አልነበረባቸውም በማለት ቅር ተሰኝቶ ሊወቅሳቸው ይችላል። በመሠረቱ እሳቸውም መሳሳታቸውን አልሸፈኑም። ዘማቹን ሠራዊት ባሰናበቱበት ዕለት ባደረጉት ንግግር፣ በመንግሥታት ማህበር ላይ ዕምነት አሳድረው ለጦር ዝግጅቱ

መዘግየታቸውን ገልጸዋል። ይሁን እንጂ፣ በደረሰው ሁኔታ ላይ አንድ ዓይነት የፍርድ አስተያየት ለመስጠት በዘመኑ ከነበረው አስተሳሰብና አሠራር ማዛመድ ያስፈልጋል። በጥንታዊቷ ኢትዮጵያ ባሕልና ልማድ በነገሥታቱና በመሳፍንቱ ሥርዓት፣ ተከትትተው ያደጉት ተፈሪ መኰንን፣ በመንግሥታት መሪዎች መካከል የሚደረግ ግንኙነት ሁሉ፣ በእውነተኛ ወዳጅነት ላይ የሚመረኮዝ ብቻ ሳይሆን፣ ዕምነትና ቃል ኪዳን እንደ ሃይማኖት የሚከበርበት መሆን እንዳለበት ከልባቸው የሚያምኑ ናቸው። በዚህም አኳኋን፣ አንድ የአውሮፓ መንግሥት ሾሞ የሚልካቸውን እንደራሴ (አምባሳደር) የሚቀበሉትም ሆነ የሚያስተናግዱት በመሪው ስም አድርገው ስለሆነ፣ በዲፕሎማሲ ሥራ ከእውነትና ከጨዋነት በስተቀር ሸርና ቅጥፈት መኖሩን በዚያን ዘመን አያውቁም ነበር። ለመንግሥታት እንደራሴዎች ስለሚሰጠው ክብርና ዕምነት፣ ተፈሪ መኰንን በዚያን ጊዜ ይከተሉት የነበረውን ይህንን አሠራር፣ ከጥንታዊው ዘመን ጀምሮ እስከ መጀመሪያው የዓለም ጦርነት ፍጻሜ ድረስ (1920 ዓ.ም) በሥልጣኔ የገፉት የአውሮፓ ታላላቅ መሪዎች ሁሉ ሲፈጽሙት የቆየ ወግና ልማድ መሆኑን ታሪክ አሳይቶናል። ከመጀመሪያው የዓለም ጦርነት ወዲህ፣ በአውሮፓ አገሮች ዘንድ፣ የውጭ አገር መንግሥታት እንደራሴዎች ለሆኑት ዲፕሎማቶች ስለሚሰጣቸው ክብርና ስለሚኖራቸው ተደማጭነት ከፍ ያለ ለውጥ ተደርጓል። በዘመናዊ አሠራር የአንድ አገር አምባሳደር በተወከለበት አገር ለፖለቲካውና ለኤኮኖሚው ግንኙነት ኃላፊነቱን ለማከናወን የዲፕሎማትነት መብቱ በሕግ የሚጠበቅለት ቢሆንም፣ እንደአለፈው ዘመን፣ የሚደረግልኝ አቀባበልና የሚሰጠኝም ክብር በአገሬ መሪ ደረጃ ነው። የምገልጸውም ሐሳብ በአገሬ መሪ ስም ነው። በሥራ ጉዳይ የማያነጋግረኝም የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ብቻ ነው ... ወዘተ ... እያለ መንደላቀቅ አይችልም።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ስለ ዲፕሎማቶች ሚና በአውሮፓ የተደረገውን መሻሻል ባለመስማት፣ ለተወሰኑ ዓመታት የቀድሞውን ልማድ ተከትለው ሲሠሩ መቆየታቸው ያስወቅሳቸዋል ለማለት ሳያስቸግር አይቀርም። እርግጥ ነው ! ጠላት ወሰን ጥሶ ከመምጣቱ በፊት፣ ንጉሠ ነገሥቱ ከዲፕሎማቶቹ የቀረበላቸውን ምክር ችላ ብለው፣ አገሪቱ ባላት አቅም የጦር ዝግጅት አድርገው ቢሆን ኖሮ፣ የኢትዮጵያን ነፃነት ለተወሰነ ጥቂት ጊዜ ማቆየት ይቻል ነበር የሚባለውን ትችት ማቃለል አይገባም። ይሁን እንጂ፣ እጅግ በተራቀቁ ዘመናዊ መሣሪያዎች፣ ከመጠን በላይ የታጠቀውን የፋሽስት የምድርና የአየር ኃይል ጦር፣ ለብዙ ጊዜ ለመመከት የሚያስችል ዝግጅት ለማድረግ፣ ኢትዮጵያ ምንም ዓይነት አቅምና ረዳት እንደሌላት አብሮ መታሰብ አለበት።



ሙሶሊኒ ኢትዮጵያን ለመውረር ከብዙ ዓመታት ጀምሮ ያዘጋጀውን
በብዙ መቶ ሺህ የሚቆጠር ጦር፤ በመርከብ አሳፍሮ ላከ፤

# ምዕራፍ ፬

## የአንድ ታዋቂ መሥፍን ክዳት
## ደጃዝማች ኃይለሥላሴ ጉግሣ

### የመሥፍኑ አጭር ታሪክ፤

የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት የነበሩት የአፄ ዮሐንስ ፬ኛ የልጅ ልጅ፤ የራስ ጉግሣ አርዓያ ልጅ የሆኑት ደጃዝማች ኃይለሥላሴ ጉግሣ፤ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ሁለተኛዋን ሴት ልጅ ልዕልት ዘነበወርቅን በሕግ አግብተው ከሸዋ ንጉሣዊ ቤተሰብ ጋር ተቀላቅለው ነበር። ባለመታደል ጋብቻቸው እጅግ በደመቀ በዓል በተፈጸመ በዘጠነኛው ወር በጽንስ ምክንያት ልዕልት ባለቤታቸው በድንገት ሲሞቱባቸው፤ በአዲስ አበባና በትግራይ ከፍ ያለ ኃዘን ሆነ። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴም በጣም የሚያቀርቧቸው ልጃቸው በአሥራ ስድስት ዓመት ዕድሜያቸው በድንገት በመሞታቸው፤ እጅግ የመረረ ኃዘን ተሰምቷቸው ነበር። በቀብሩ ሣልስት፤ ንጉሠ ነገሥቱ ለሕዝባቸው በሰጡት መግለጫ፤ « .... **በልጄ በዘነበወርቅ ሞት ኃዘኑ የጸናብኝ፦**

**፩/ በሕፃንነት ዕድሜዋ፣**
**፪/ በሙሽርነቷ ወራት፣**
**፫/ ነፍስ ጡር ሆና ሳትገላገል፣**

**ከዚህ ዓለም በመለየቷ ነው።** ይህንን እጅግ የመረረ ኃዘን አጥብቄ ብይዘው፤ በአንድ በኩል ተስፋ የሌላቸውን አሕዛቦችን መምሰል ስለሚሆንብኝ፤ በሌላ በኩል ደግሞ መሪያችሁና ጠባቂያችሁ አድርጐ ፈጣሪዬ የመረጠኝ መልካም ምሳሌም እንድሆናችሁ ስለሆነ፤ ከዚህ ከደረሰብኝ ከባዱ ኃዘን ለመታገሥ ቆርጫለሁ። እናንተም የእኔን አይታችሁ፤ በሚደርስባችሁ አደጋ ሁሉ የመረረ ኃዘን ከማድረግ እንድትቆጠቡ አደራ እላችኋለሁ .... » በማለት፤ ጥልቅ ስሜት የያዘ ማሳሰቢያ ሰጡ።

በዚያን ጊዜ የሐያ አራት ዓመት ዕድሜ የነበራቸው ወጣቱ መስፍን ደጃዝማች ኃይለሥላሴ አዲስ አበባ መጥተው ባለቤታቸውን ቀብረው በተመለሱ በጥቂት ቀናት ውስጥ፤ በሕመም ላይ ይገኙ የነበሩት አባታቸው ራስ ጉግሣ አርዓያ ስለሞቱባቸው፤ ለወደቀባቸው የተደራረበ ኃዘን ሕዝቡ እጅግ አድርጐ አዘነላቸው። ከአዲስ አበባ ቤተመንግሥትም ላልታደሉትና ኃዘን ላጠቃቸው መስፍን፤ በየዕለቱ የሚላክላቸው ማጽናኛ ብዙ እንደነበረ ይነገራል።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ከነገሡ ከአንድ ዓመት በኋላ፤ በሰኔ 9 ቀን 1924 ዓ.ም የሚወዷቸውን ልጃቸውን ለራስ ጉግሣ ልጅ ለመዳር የወሰኑት፤ ከአፄ ዮሐንስ ቤተሰቦች ጋር ዝምድና ለማስተሳሰር ብቻ ሳይሆን፤ ለሙሽራው አባት ያላቸውን



የደጃዝማች ኃይለሥላሴ ጉግሣ ክዳት፤ በይፋ ተገለጸ፡

ጥልቅ ወዳጅነት በማሰብ ነው እየተባለ የሚወራው ትክክል ነው ለማለት ይቻላል። የአልጋወራሽ ተፈሪ መኰንን ዋና ባላጋራ የሆኑትን ልጅ ኢያሱ ሚካኤልን ለመያዝ ከአራት ዓመታት በላይ በየጫካውና በየበረሀው ያ ሁሉ ውጊያ ቢደረግም፣ የተፈለገው ውጤት ሳይገኝ ቆይቶ ነበር። በመጨረሻው ልጅ ኢያሱን ከተደበቁበት ቦታ አግኝቶ ለማሰርና እፎይ ለማለት የተቻለው፣ በራስ ጉግሣ አርዓያ ትብብርና እርዳታ ስለሆነ፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ይህንን ውለታ በቀላሉ የሚዘነጉት አልነበረም። የዚህን ታሪክ ሂደትና አፈጻጸም ከዚህ ቀደም ላልሰሙት ወይም ላላወቁት በአንድ ፓራግራፍ ባጭሩ ማብራራት የሚያስፈልግ ይሆናል።

ልጅ ኢያሱ ለብዙ ዓመታት ሲያደርጉት የቆየውን የሽፍትነት ሕይወት መቀጠል ስለአቃታቸው፣ በመጨረሻ ከነበሩበት ከአዳል በረሀ ወጥተው ወደ ትግራይ በመሻገር፣ መቀሌ ከሚገኘው ከታላቅ እህታቸው ከወይዘሮ ተዋበች ሚካኤል ቤት ገብተው ተደበቁ። ወይዘሮ ተዋበች የወሎው ባላባት የንጉሥ ሚካኤል ልጅ ሲሆኑ፣ ባለቤታቸው ደግሞ፣ የትግራይ የአንዱ ክፍል መስፍን የሆኑት ልዑል ራስ ሥዩም መንገሻ ነበሩ። የልጅ ኢያሱ መቀሌ መድረስ እንደ ተሰማ፣ ራስ ሥዩም እጃቸውን ይዘው ደሴ ላይ ለሰፈረው ለፊታውራሪ ሀብተጊዮርጊስ ጦር እንዲያስረክቡ ከአልጋ ወራሽ ተፈሪ የተላለፈላቸውን ትእዛዝ ሳይፈጽሙ፣ ጉዳዩ በሽምግልና ታይቶ ሰላማዊ መፍትሔ ቢሰጠው አይሻልም ወይ? የሚል አቋም አሳዩ። በዚህ ጊዜ፣ ራስ ሥዩም የታዘዙትን ለመፈጸም ፈቃደኛ እንዳልሆኑ ስለተቆጡ፣ አልጋወራሽ ተፈሪ ፊታቸውን ወደ ሌላው የትግራይ መስፍን ወደ ልዑል ራስ ጉግሣ አርዓያ መልሰው፣ ልጅ ኢያሱን ይዘው እንዲያስረክቧቸው ጠየቋቸው። ጉግሣ አርዓያ የአጐታቸው ልጅ የሆኑት ሥዩም መንገሻ እምቢታ ያሳዩበትን ጉዳይ እሳቸው ተቀብለው፣ የአልጋወራሽ ተፈሪን ትዕዛዝ ለማክበርና ለመፈጸም ዝግጁ ሆኑ። በዚህም መሠረት፣ «... ኢትዮጵያን ለማስለም የተነሣውን ኢያሱን፣ ጳጳስ ገዝቶታል። ሕዝብ አልቅሶበታል። ስለዚህ እጁን ይዤ ለፍርድ እንዲቀርብ ባደርግ፣ እግዚአብሔር አይጣላኝም። ሰውም አያዝንብኝም በሚል መንፈስ አቋማቸውን አጠንክረው ልጅ ኢያሱ በመጨረሻ ከተሸሸጉበት " ስለዋ - ቅብፅያ " ከተባለው ገዳም አስወጥተው በመያዝ፣ ደሴ ከተማ ላይ ለራስ ተፈሪ መኰንን እና ለፊታውራሪ ሀብተ ጊዮርጊስ አስረከቡ። በዚህ መልካም ውጤት የወደፊቱ ንጉሠ ነገሥት እጅግ ተደስተው፣ ለባለውለታው ለጉግሣ አርዓያ ከከፍተኛ ሽልማት ጋር በትግራይ ውስጥ ተጨማሪ ግዛት ሲሰጧቸው፣ ተባባሪ አልሆኑም ለተባሉት ለሥዩም መንገሻ ግዛታቸው ተቀንሶ ወደ አዲስ አበባ እንዲሄዱና ሳይታሰሩ በግዞት መልክ እንዲቆዩ ተደረገ። *

አሁን ወደ ተነሣንበት ጉዳይ እንመለስና ከአፄ ዮሐንስ አራተኛ ቀጥታ ዘርፍ የተወለዱት፣ ቀጥሎም የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አማች የነበሩት መስፍን፣ ኢትዮጵያን በጦር ወግቶ ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ ለመጣብን የፋሽስት ጠላት ተባባሪ በመሆን የፈጸሙትን ድርጊት፣ ታሪክ በየጊዜው ሳያወሳው ሊያልፍ የሚችል አልሆነም።

እርግጥ ነው! በዚያን ጊዜ ለጠላት ገብተው ጠላትን ሲያገለግሉ የነበሩ ብዙ ታላላቅ ሰዎች መኖራቸው እየታወቀ፣ የደጃዝማች ኃይለሥላሴ ጉግሣ ክዳት ከነዚህ

* ስለዚህ ጉዳይ በዝርዝር የተጻፈውን " ተፈሪ መኰንን " በተባለው መጽሐፍ ገጽ 396 ተመልከት ።

ሁሉ የተለየና ገናና የሚያደርገው ምክንያት ምን ይሆን ? የሚል ጥያቄ አንዳንድ ሰዎች ማቅረባቸውን ማስታወስ ያስፈልጋል፡፡ ስለዚህም፤ እስከዛሬ ድረስ በተደረገው የታሪክ ምርምር የደጃዝማች ኃይለሥላሴ የክዳት ዓይነትና አፈጻጸም፤ ከሌሎቹ ሁሉ የተለየ የሚያደርገው በቂ ምክንያት መኖሩ መታወቅ አለበት፡፡ ደጃዝማች ኃይለሥላሴ ጉግሣ፤ ለፋሽስት መንግሥት ተባባሪነታቸውን በመግለጽ

የመጀመሪያው መስፍን ብቻ ሳይሆኑ፤ ከጠላት ጋር ተሰልፈው አገራቸውን ለመውጋት የፋሽስት ዩኒፎርም ለመልበስም የመጀመሪያው ናቸው፡፡

ኢትዮጵያን ለመውረር የጦሩ ዋና አዛዥ የሆነው ጄኔራል ኤሚሊዮ ደ-ቦኖ በጻፈው ማስታወሻ ላይ፤ ደጃዝማች ኃይለሥላሴ ጉግሣ አገሩን ከድቶ የኛ ወገን ለመሆን አድዋ ላይ ከሚገኘው የጣልያን ቆንስላችን ጋር የምሥጢር ንግግር የጀመረው ጦርነቱ ከመከፈቱ ቢያንስ ከአምስት ወራት በፊት ነበር ይላል፡፡፡ ከመስፍኑ ከጉግሣ የቀረበልን ሐሳብ ምን ያህል አስተማማኝ መሆኑን በማጥናት ጥቂት ጊዜ ከቆየን በኋላ፤ እ.ኤ.አ በጥቅምት ወር 1935 ዓ.ም መጀመሪያ ላይ፤ ከዳተኛው አሥር ሺህ ተዋጊዎች አስከትሎ፤ በአዲግራት በኩል መምጣቱ ተነገረን፡፡ እኛም ይህን ትልቅ ዜና ለመሪያችን ለዱቼ ሙሶሊኒ በቴሌግራም ስናስተላልፍ፤ « ... በጣም ጥሩ ውጤት ነው ... » የሚል የሞቀ መልስ አገኘን፡፡ ይሁን እንጂ፤ ደጃዝማች ኃይለሥላሴ ጉግሣ አስከትሏቸው የመጡት ተዋጊዎች ቁጥራቸው ከሺህ ሁለት መቶ የሚበልጡ አልነበሩም፡፡ አሥር ሺህ (10.000) ናቸው ተብሎ ከተነገረን ውስጥ ሌሎቹ የት ደረሱ ? ብለን ብንጠይቅ፤ በጉዞው ላይ ጉግሣን አንከተልም ብለው እየከዱ ወደየአገራቸው ስለተመለሱ ነው የሚል መረጃ አገኘን፡፡ *

መስፍኑ ጉግሣ እኔ በተቀበልኩት ጊዜ የሚከተለውን ነገረኝ፡፡

1. የኢትዮጵያ ሕዝብ ከጣልያን ጋር ጨርሶ ጦርነት አይፈልግም፡፡ ጦርነቱን የሚፈልጉት ንጉሠ ነገሥቱ ብቻ ናቸው፡፡ እሳቸውም እስከዚህ ለመድፈር የተነሡት፤ እንግሊዞች ብዙ መሣሪያዎች ይሰጡዎታል እያሉ አንዳንድ የስለላ ሥራ የሚሠሩ ሰዎች ስለመከሯቸው ነው፡፡

2. እኔ አጥብቄ የማሳስበው፤ ከዛሬ ጀምሮ (ጥቅምት 17/1935 ዓ.ም) በትግራይ ውስጥ መቀሌን ለመያዝ ፈጣን እርምጃ መውሰድ ያስፈልጋል ብዬ ነው፡፡ ጦሩንም እኔው ራሴ በመምራት መቀሌን ለመያዝ ተዘጋጅቻለሁ አለኝ፡፡ በበኩሌ፤ መስፍኑ ጉግሣን መከርኩት፡፡ « ... በጥድፊያ የሚወሰድ እርምጃ ሁሉ ውጤቱ መልካም አይሆንም፡፡ ከሁሉ አስቀድሞ በመቀሌ በኩል ሊኖር የሚችለውን የተከላካይ ጦር አቅም መመዘንና፤ መገናኛዎቹን ሁሉ ማጠንከር ያስፈልጋል፡፡ ስለዚህ፤ አንተ ከዛሬ ጀምሮ ድምጽህን አጥፍተህ፤ ትዕዛዝ ለመቀበል ዝግጁ ሆነህ በእርጋታ ጠብቀኝ፡፡ አስፈላጊውን ሁሉ ወስኜ አስታውቅሃለሁ አልኩት ... » ቀጥሎም ለዱቼ በላኩት ቴሌግራም፤ መቀሌን በአስቸኳይ ለመያዝ ከመስፍኑ የቀረበልኝን

---

* እነዚህ ሰዎች፤ የአፄ ዮሐንስ ልጅ እንዴት አገሩን ከድቶ ለጠላት ይገባል? ብለው በመቆርቆር ያዘኑና፤ ኋላም ወደ ማይጨው ሄደው እንደዘመቱ ታውቋል፡፡

ሐሳብና የእኔንም አስተያየት ገለጽኩለት። መሪያችን (ዱቼ) ወዲያውኑ በሰጠኝ መልስ፤ « ... **እንዳልከው መቀሌን ለመያዝ መጀመሪያ የመገናኛ ዝግጅቶቹን ማጠናቀቅ አለብህ። ቀጥሎ ደግሞ ዘመቻውን የምትጀምረው እኔ ወስኜ በምነግርህ ቀን ነው** ... » አለኝ።

ሙሶሊኒ፤ እንደ እ.ኤ.አ ህዳር 3 ቀን 1935 ዓ.ም፤ መቀሌ እንዲወረር የሰጠው ትእዛዝ ከመፈጸሙ በፊት፤ ደጃዝማች ኃይለሥላሴ ጉግሣ በዱቼና በንጉሡ በቪክቶር አማኑኤል ሳልሣዊ መልካም ፈቃድ ራስ ተብለው የትግራይ ጠቅላይ ገዥ እንዲሆኑ መሾማቸው በይፋ ተነገረ። በተጨማሪም መላ ኢትዮጵያን ለመያዝ በሚደረገው ዘመቻ የዋናው አዛዥ የጄኔራል ደ-ቦኖ የጦሩ አመራር አማካሪ እንዲሆኑ ተደረገ። በዚህ አኳኋን ህዳር 8 ቀን 1935 ዓ.ም የንጉሠ ነገሥት ዮሐንስ አራተኛ መናገሻ ከተማ የነበረው " **መቀሌ** " በጠላት እጅ ሲወድቅ፤ ራስ ኃይለሥላሴ ጉግሣ አርዓያ የተሰጣቸውን የፋሽስት የጦር ልብስ ለብሰው በግንባር በመገኘት የደስታው ተካፋይ ከመሆናቸውም በላይ፤ በመቀሌ ከተማ እምብርት ላይ በኢትዮጵያ ሰንደቅ ዓላማ ቦታ የጣልያንን ባንዲራ የሰቀሉ ራሳቸው ሆኑ።

በኢትዮጵያ ላይ ጦርነቱ ከተከፈተ አንድ ወር ተኩል በማይሞላ ጊዜ ውስጥ፤ ከትግራይ ክፍለ ሀገር አድዋና አንቲጮ፣ አዲግራትና መቀሌ ከተያዙ በኋላ፤ ወደ ማህል ኢትዮጵያ መደረግ የነበረበትን ዘመቻ አዘግይተሃል በማለት፤ ዱቼ ሙሶሊኒ የጦሩን ዋና አዛዥ **ጄኔራል ኤሚሊዮ ደ-ቦኖን ሽሮ፤ በምትኩ ማርሻል ባዶግሊዮን ሾመ።** ይህም ለውጥ ቢደረግ፤ ለራስ ኃይለሥላሴ ጉግሣ የተሰጠውን ክብር የሚነካ አልነበረም። ይልቁንም አዲሱ የጦር አዛዥ ቀደም ሲል ጄኔራል ደ-ቦኖ እንደ ጀመረው ሁሉ፤ የትግራዩን መሥፍን በጠቅላይ ገዥነታቸው ብቻ ሳይሆን፤ ከመቀሌ እስከ አዲስ አበባ በተደረገው ዘመቻ ሁሉ የአማካሪነት ተግባራቸውን እንዲቀጥሉ አድርጓል። በመጨረሻም፤ እ.ኢ.ት.አ ሚያዝያ 27 ቀን 1928 ዓ.ም የሙሶሊኒ ዋና የጦር አዛዥ ማርሻል ባዶግሊዮ ድል አድራጊ ሆኖ በከፍተኛ አጀብ ከኢትዮጵያ ዋና ከተማ አዲስ አበባ ሲገባ፤ ከክብር ተከታዮቹ ተቀዳሚ ሆነው የታዩት ኃይለሥላሴ ጉግሣ ነበሩ። በኢትዮጵያ ላይ የሙሶሊኒ መንግሥት በነገሠበት ዘመን መጀመሪያ በጨካኙ በግራዚያኒ፤ ቀጥሎም በዱካ ዳኦስታ አገዛዝ፤ ኃይለሥላሴ ጉግሣ ከትግራይ ገዥነታቸው ይልቅ ለፋሽስት መሪዎች የቅርብ አማካሪ በመሆን የሰጡት አገልግሎት ምን ያህል ጠቃሚ እንደነበረ፤ ሁሉም በየበኩላቸው መስክረውላቸዋል።

እንግዲህ ! ከዚያ አገራችን ከደረሰባት የመከራ ዘመን በኋላ፤ የዓለም ሰላም ባልታሰበ መንገድ ሲደፈርስና ሙሶሊኒ የሂትለር ግብረ አበር ሆኖ እንግሊዝንና ፈረንሣይን ሲወጋ፤ የኢትዮጵያ ነፃነት የመመለሱ ዕድል የተፋጠነ ሆነ። በዚህ ጊዜ ከዳተኛው መስፍን የወደፊት ሕይወታቸው ወዴት አቅጣጫ እንደሚያመራ ስላልታያቸው፤ ትልቅ ጭንቅ ሆነባቸው። ፋሽስቶች የነገሯቸው ሁሉ እውነት ከሆነ፤ በሰሜን ኢትዮጵያ የተከማቸውን የሙሶሊኒን ጦር እንግሊዞች ድል ለማድረግ ብዙ ዓመት ሊወስድባቸው ይችላል የሚል ተስፋ አደረባቸው። በኢትዮጵያውያኖች በኩል ያለውን መንፈስ ሲመለከቱ ደግሞ፤ እንግሊዞች በቅርብ ጊዜ ውስጥ ፋሽስትን ደምስሰው አገሪቱን ነፃ ሊያወጡ እንደሚችሉ ተሰማቸው። ስለዚህ አውጥተው አውርደው የታያቸው መፍትሔ፤ እንግሊዞች በፍጥነት አሸንፈው ከመጡ፤ ከእነሱ ጋር የመተባበር መንፈስ በማሳየት የወደፊት ዕድሌን ለማዘጋጀት ጊዜ ይሰጠኛል የሚል ተስፋ ዘረጉ። ይህ በመጨረሻው የተለሙትም ዕቅድ፤ ወደተግባር የመለወጥ መልክ አሳያቸው። ለፋሽስት መሪዎች ያላቸው ልባዊ



ልዕልት ዘነበወርቅ ኃይለሥላሴ፤ የደጃዝማች ኃይለሥላሴ ጉግሳ ባለቤት

ፍቅር እንደ ተጠበቀ ሆኖ፤ እንግሊዞችን ለመማረክ ያሳዩት የጋለ መንፈስ አንድ ዕድል ከፈተላቸው። አሥመራ ላይ የተቋቋመው የእንግሊዝ ወታደራዊ አስተዳደር፤ የትግራይን ክፍለሀገር ቀድሞ እንደነበረው በሁለት ክፍሎ፤ የምዕራቡን አውራጃዎች ራስ ሥዩም መንገሻ፤ የምሥራቁን ደግሞ ደጃዝማች ኃይለሥላሴ ጉግሣ እንዲገዙ በመወሰን፤ ለመላው ትግራይ ሕዝብ መግለጫ በተነ። የእንግሊዝ ወታደራዊ አስተዳደር፤ ከነዚህ ከታወቁት ሁለት ሰዎች የሚጠብቀው በአስተዳደር ጉዳይ ብቻ ሳይሆን፤ በጠቅላላው በሰሜን በኩል የሰፈረውን የፋሽስት ጦር በሙሉ ለማጥፋት እስከሚቻልበት ጊዜ ድረስ ሕዝቡን በማስረዳትና ለዘመቻ በማዘጋጀት እንዲረዱ ነበር።

ራስ ሥዩም መንገሻ ወዲያውኑ እርምጃ ወስደው የጣልያንን ጦር እያሳደዱ በመውጋት፤ በተለይም አምባላጌን ለመያዝ በተደረገው ጦርነት ከፍ ያለ ተጋድሎ ሲያደርጉ፤ ኃይለሥላሴ ጉግሣ ምንም ዓይነት እንቅስቃሴ ሳያሳዩ ቀሩ። ይልቁንም በተሰጣቸው ግዛት ውስጥ፤ ሥራ ፈቶችና ቀማኞች እየተስፋፉ የሕዝቡን ፀጥታ ሲያውኩ ዝም ብለው ተመልከተዋል በመባል በብዙ ተወቀሱ። ደጃዝማች ኃይለሥላሴ ከእንግሊዝ ወታደራዊ አስተዳደር የተጣለባቸውን አደራ ለመፈጸም ችላ ያሉበት ምክንያት ምን እንደሆነ በዚያን ጊዜ እንደተወራው፤ በሰሜን በኩል ተከማችቶ የነበረው የፋሽስት ጦር በብዛቱም ሆነ በዝግጅቱ እጅግ ከፍ ያለ ስለሆነ፤ ምናልባት እንግሊዞችን አሸንፎ ትግራይን እንደገና በመያዝና ከቅኝ ግዛቱ ከኤርትራ ጋር አቀላቅሎ ለመግዛት ይችል ይሆናል በሚል ተስፋ ነበር ይባላል። ይህ አንዱ ምክንያት እንደሚሆን ቢታሰብም፤ ሌላው ደግሞ ኃይለሥላሴ ጉግሣን ትልቅ ጭንቅ ውስጥ የከተታቸው ነገር መኖሩ ግልጽ ነው። ከዳተኛ በመሆናቸው ከጠላት ጋር በመሰለፍ አገራቸውን ወግተው ያስያዙ ሰው ስለሆኑ፤ አሁን ተመልሰው በሕዝብ ፊት ፋሽስትን ለማውገዝና፤ ኢትዮጵያን ነፃ ለማውጣት ከመጡት ከእንግሊዞች ጋር ተሰልፌያለሁ ለማለት፤ የሚናገሩበት የአንደበትና የሞራል ብርታት አጥተው ይሆናል ለማለት ይቻላል።

እ.ኢት.አቆ ሚያዝያ 27 ቀን 1933 ዓ.ም፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የነፃነት ችቦ እያበሩ ከመናገሻ ከተማቸው ሲገቡ፤ የታወቁት ከዳተኛ እጅግ አስገራሚ የሆነ ቴሌግራም ለንጉሠ ነገሥቱ ከመቀሌ ወደ አዲስ አበባ ላኩ።

" ... ከአምስት ዓመታት በኋላ ጠላታችን ወድቆ የነፃነት ባንዲራችን በመላው ኢትዮጵያ ለመውለብለብ በመብቃቱ፤ ለእግዚአብሔር ለምናቀርብለት ምስጋና ገደብ አንሰጠውም። ... ጠላታችንን ከአገራችን ለማስወጣትና ነፃነታችንን እቦታው ለመመለስ፤ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ላደረገልን ውለታ ምሥጋናዬ እጅግ የላቀ ነው። በዚህ በምልክልዎ ቴሌግራም፤ ዘውድዎ በመመለሱና በአገራችን ላይ የነፃነት ባንዲራችን በመውለብለቡ፤ የራሴንና በመቀሌ የሚገኘውን የሕዝቤን ደስታ እገልጽልዎታለሁ ... "

ፊርማ ራስ ኃይለሥላሴ ጉግሣ

በዚህ ቴሌግራም ላይ የሠፈረውን የሐሳብ አገላለጽና አቀራረብ ስንመለከት፤ በኢትዮጵያ ሥርዓትና ባሕል፤ በተለይም በንጉሣዊ ቤተሰቦችና በታላላቅ ሰዎች ዘንድ የሚሠራበትን የተለመደውን የአጻጻፍና የአነጋገር ሥልት ያልተከተለ መሆኑን ለመገንዘብ አያዳግትም። ከሁሉ በፊት እኔ "ራስ ኃይለሥላሴ ጉግሣ" ብሎ

ለመፈረም፤ ይህ ሹመት የተገኘው ከጠላት መሪ እንጂ፤ ከኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ያልተሰጠ ስለሆነ፤ በትልቅ ሞያ የተገኘ ማዕረግ አስመስሎ መጠቀም ከመስፍኑ የሚጠበቅ አልነበረም። ይሁን እንጂ፤ ይህን ቴሌግራም ያረቀቁት ራሳቸው ስለሆኑ፤ ሐሳባቸውን በፌዝ መልክ ማቅረባቸው፤ ከንጉሠ ነገሥቱ ጋር ወደፊት ለመታረቅ ምንም ዓይነት ተስፋ የሌላቸው መሆናቸውን የሚያመለክት ነው የሚል አስተያየት ተሰጥቶበታል። ንጉሠ ነገሥቱም ለዚህ ቴሌግራም እንዳችም መልስ አለመስጠታቸው ታውቋል።

ቀደም ሲል እንደተጠቀሰው፤ የፋሽስትን ጦር ከመላ ኢትዮጵያ ለመደምሰስ የታላቋ ብሪታንያ ወታደራዊ ድርጅት በሚያደርገው ጥረት፤ ራስ ሥዩም መንገሻ ከፍተኛ ትብብር ሲያደርጉ፤ ደጃዝማች ኃይለሥላሴ ጉግሣ የሚጠበቅባቸውን ሁሉ ሳይፈጽሙ በመቅረታቸው፤ የእንግሊዝ ጊዜያዊ አስተዳደር የሚከተለውን ውሳኔ ሰጠ።

" ... ራስ ኃይለሥላሴ ጉግሣ በምሥራቅ ትግራይ የተሰጣቸውን ኃላፊነት የማይፈጽሙና ከእንግሊዝ ወታደራዊ አስተዳደር ጋር ምንም ዓይነት ትብብር ማድረግ ያልቻሉ ወይም ያልፈለጉ በመሆናቸው፤ ከዛሬ ዕለት ጀምሮ ከሥራቸው ተወግደው፤ ለጊዜው አሥመራ ከተማ በጥብቅ እንዲቆዩ ተወስኖባቸዋል። የምዕራቡ ትግራይ አውራጃዎች ገዥ የሆኑት ራስ ሥዩም ግን፤ ከእንግሊዝ ወታደራዊ አስተዳደር ጋር በሚያስፈልገው ሁሉ እየተባበሩ፤ ፋሽስትን ለማስለቀቅ በተደረገው ዘመቻ ሁሉ ጠቃሚ የሆነ እርዳታ ያበረከቱ በመሆናቸው፤ ከዛሬ ጀምሮ የመላው ትግራይ ገዥ ሆነው እንዲሠሩ ተደርጓል ... "

ይህ ውሳኔ በአዋጅ መልክ ተዘጋጅቶ ለመላው ትግራይ ሕዝብ በተነገረ ጊዜ፤ ደጃዝማች ኃይለሥላሴ እንግሊዞች እጄን ይዘው ለኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ያስረክቡኛል ብለው ስለሠጉ፤ ከዚሁ ዕለት ጀምሮ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት የፖለቲካ ጥገኝነት ይስጠኝ ሲሉ አመለከቱ።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ነፃነት ተገኝቶ አዲስ አበባ ከተመለሱ በኋላ፤ በሰሜን ኢትዮጵያ ላይ ያለው የእንግሊዝ ጊዜያዊ ወታደራዊ አስተዳደር፤ ደጃዝማች ኃይለሥላሴ ጉግሣን የምሥራቅ ትግራይ ገዥ አድርጉ መሾሙን ሲሰሙ፤ እንዴት ከጠላታችን ከፋሽስት መንግሥት ጋር ሆኖ ለወጋንና ብዙ ጉዳት ላደረሰብን ሰው ይህን ኃላፊነት ትሰጣላችሁ? ... በማለት እጅግ የጠነከረ ቅሬታቸውን አሰምተው ነበር። ከዚህም አያይዘው፤ ኃይለሥላሴ ጉግሣ የፋሽስት ወገን ሆኖ በአገራችን ላይ የፈጸመው ወንጀል ብዙ ስለሆነ፤ በኢትዮጵያ ሕግ መሠረት ፍርድ እንዲቀበል ወደ ኢትዮጵያ ይመለስልን ሲሉ ደጋግመው ጠየቁ።

በዚያ በሁለተኛው የዓለም ጦርነት ዘመን ምንም እንኳ ፋሽስት ድል ሆኖ የኢትዮጵያም ነፃነት ተመልሷል ቢባልም፤ የአገሪቱን አስተዳደር ሥልጣን የያዙት እንግሊዞች ስለሆኑ፤ ከንጉሠ ነገሥቱ የሚቀረብላቸውን ጥያቄ ሁሉ በጥሞና አያዳምጡም ነበር። በሰሜን ኢትዮጵያ የተቋቋመው የእንግሊዝ ወታደራዊ አስተዳደር ማንንም ሳያማክር ለደጃዝማች ኃይለሥላሴ ጉግሣ በሰጠው ኃላፊነት፤ ምን ያህል እንደተሳሳተ በጥቂት ወራት ውስጥ በሚገባ ተረድቶታል። ሆኖም፤ ሰውየውን ከሹመታቸው ሽሮ አሥመራ ላይ በቁጥጥር እንዲቆዩ ከማድረግ በስተቀር፤ ወደ ኢትዮጵያ ተመልሰው ለፍርድ እንዲቀርቡ ከኢትዮጵያ ንጉሠ

ነገሥት የተጠየቀውን ለመፈጸም አልፈለገም። ለዚህም፣ እየደጋገመ የሰጠው መልስ፣ ኃይለሥላሴ ጉግሣ የፖለቲካ ጥገኝነት እንዲሰጣቸው ስለጠየቁ፣ ሰውየውን ይዞ ለኢትዮጵያ መንግሥት ለማስረከብ የእንግሊዝ ሕግና ልማድ አይፈቅድም የሚል ነበር።

ንጉሠ ነገሥቱ ከነፃነት በኋላ ባቋቋሙት ካቢኔ ውስጥ፣ የውጭ አገር ትምህርት ተምረው ከመጡት መካከል፣ ብላቴን ጌታ ሎሬንሶ ታዕዛዝና አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ፣ እንግሊዞች የደጃዝማች ኃይለሥላሴ ጉግሣን ጉዳይ በፖለቲካ ጥገኝነት የመመልከት መንገድ መያዛቸው ትክክል አይደለም በማለት የሚከተለውን አስተያየት ለጃንሆይ አቀረቡ።

1. ኃይለሥላሴ ጉግሣ ኢትዮጵያን መክዳት ብቻ ሳይሆን፣ ከጠላት ጋር በይፋ ተሰልፎ አገሩን የወጋ "ከሐዲ" እንጂ የፖለቲካ ሰው ተብሎ የሚቆጠር አይደለም።

2. ኢትዮጵያና ታላቋ ብሪታንያ የቃል ኪዳን ስምምነት አድርገው፣ የጋራ ጠላታቸው ከሆነው ከፋሽስት ጋር በሚዋጉበት በአሁኑ ሰዓት፣ አሁንም የጠላታችን የፋሽስት ወገን መሆኑ መረጃ ለተገኘበት ለኃይለሥላሴ ጉግሣ ተገቢውን ፍርድ እንዲቀበል ከማድረግ በስተቀር፣ የፖለቲካ ጥገኝነት ለመስጠት መታሰብ የለበትም።

3. ታላቋ ብሪታንያ ምንም እንኳ ለሰው ልጅ መብትና ነፃነት፣ ለዴሞክራሲ አስተዳደርና ትክክለኛ ፍርድ ስትታገል የኖረች ብትሆንም፣ አገራቸውን ከድተው የጠላት መሣሪያ በመሆን ከፍተኛ ወንጀል ለፈጸሙት ሰዎች፣ የፖለቲካ አመለካከት በማድረግ እስከዚህ ትሳሳታለች ብላ ኢትዮጵያ አታምንም።

እነዚህ ከዚህ በላይ የተገለጹትን ዋና ዋና ነጥቦች በመመርኮዝ፣ ንጉሠ ነገሥቱ ጥያቄያቸውን አድሰው የታላቋ ብሪታኒያ መንግሥት ደጃዝማች ኃይለሥላሴ ጉግሣን ለፍርድ እንዲያስረክባቸው አሳሰቡ።

በዚያን ጊዜ በአዲስ አበባ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር የነበረው ሚስተር ሮበርት ሐው፣ (Robert Howe) ይህንን የንጉሠ ነገሥቱን ጥያቄ ለሚስተር አንቶኒ ኤደን (Anthony Eden) የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ያስተላለፈው፣ " ... ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ከዳተኛው ጉግሣ ለኢትዮጵያ መንግሥት ተሰጥቶ ፍርዱን እንዲቀበል ያቀረቡትን ሐሳብ እደግፋለሁ ... " ከሚል አስተያየት ጋር ነበር። ሚስተር ሐው፣ የንጉሠ ነገሥቱ ጥያቄ የሚደገፍ ነው የሚልበትን ምክንያት በላከው ደብዳቤ ላይ እንደሚከተለው አስረድቷል። " ... እንደሚታወቀው ሁሉ የንጉሠ ነገሥቱ አማች የነበረው ደጃዝማች ኃይለሥላሴ ጉግሣ፣ በኤርትራ የሰፈረው የፋሽስት ጦር ሰሜን ኢትዮጵያን ከመውረሩ በፊት፣ ከጠላት ጋር ተላልኮ በመስማማት ተከታዮቹን ይዞ በዘመቻው የተካፈለና አገሩን ያስያዘ ነው። በተጨማሪም የመቀሌ ከተማ በፋሽስት እጅ ሲወድቅ፣ እሱ ራሱ (ጉግሣ) የጣልያንን ባንዲራ በመስቀል፣ ለጠላት ታማኝነቱን የገለጸ ነው። ይህ ሰው የፋሽስት መሣሪያ ሆኖ በፈጸመው ሁሉ፣ በኢትዮጵያ ላይ ትልቅ ጉዳት አድርሷል። ዛሬ ፋሽስት ድል ሆኖ ነፃነታቸውን የተቀበሉት ኢትዮጵያውያኖች ይህን መሰል (ወይም ተወዳዳሪ) የሌለው የአገር ከዳተኛ ትክክለኛውን ፍርድ እንዲያገኝ



ደጃዝማች ኃይለሥላሴ ጉግሣ ለፋሽስት ታማኝነታቸውን ካስመሰከሩ በኋላ፤
“የልዑል ራስነት” ማዕረግ ከሙሶሊኒ እንደራሴ ሲቀበሉ፤

አጥብቀው ይጠይቃሉ። የዚህንም ውጤት ለማየት ለአገራቸው ነፃነት መመለስ ዋና ረዳታቸው የሆነው የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ምን ያህል እንደሚተባበር ለማወቅ በትልቅ ጉጉት ይጠብቃሉ። በተጨማሪም አስተያየታቸውን እያስፋፉ ሲናገሩ፤ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ከፋሽስት ጋር ተዋግቶ የኢትዮጵያን ነፃነትና የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ዘውድ ያስመለሰው ትክክለኛ ፍርድ ነው ብሎ ከልቡ አምኖበት ከሆነ፤ ድል የሆነውም የፋሽስት ጦር ወደፊት እንደገና ተመልሶ ያንሰራራ ይሆናል በማለት የሚሠጋ ካልሆነ፤ ይህን የጠላታችን መሣሪያ ሆኖ የጉዳንን ወንጀለኛ ለፍርድ እንዲቀርብ ለማድረግ፤ ይህን ያህል የሚያመነታበት ምክንያት አይታየንም ብለው ምሬታቸውን ይገልጻሉ። ስለዚህ የንጉሠ ነገሥቱንና የመንግሥታቸውን በጠቅላላውም የአብዛኛውን የኢትዮጵያ ሕዝብ አስተያየትና ስሜት በመረዳት፤ ቀጥሎም የጉግሣ ጉዳይ በከሀዲነት እንጂ በፖለቲካ መልክ መታየት እንደሌለበት በማመን፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የጠየቁት እንዲፈጸም እደግፋለሁ ... " ሲል የእንግሊዝ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ማመልከቻውን ደምድሟል።

ከዚህ በላይ እንደታየው በኢትዮጵያ የታላቋ ብሪታንያ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር የሆነው ሮበርት ሐው፤ ኃይለሥላሴ ጉግሣ ለንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት ተሰጥተው ለፍርድ እንዲቀርቡ የበኩሉን ድጋፍ በመስጠት ብዙ ደክሞ ነበር። ነገር ግን በዚያን ሰዓት የዓለም ጦርነት የሚካሄድበት የመከራ ዘመን ስለሆነ፤ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት የጦር ካቢኔ የከሀዲውን ጉዳይ በሕግ ረገድ በትክክል አጥንቶ ለመወሰን የሚያመቸው ጊዜ አልሆነም። በመጨረሻው የጉግሣ ጉዳይ ለጊዜው አንድ ዓይነት ውሳኔ ተሰጥቶት፤ ሰውየው ከነቤተሰቦቻቸው የእንግሊዝ ግዛት ወደሆነው ወደ ሲይሽል (Seychelles) ተልከው፤ በጥበቃ እንዲቆዩ ተደረገ። ንጉሠ ነገሥቱም የኢትዮጵያ ነፃነት ከተመለሰበት ጊዜ ጀምሮ ለአንድ ዓመት ተኩል ያህል ባለማቋረጥ፤ ከሀዲው ለፍርድ እንዲቀርብላቸው የጠየቁትን የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ለጊዜው ሳይቀበለው በመቅረቱ እጅግ ቢያዝኑም፤ በዓለም ላይ የተቀጣጠለው ጦርነት ቆሞ፤ ሰላም በሚመሠረትበት ጊዜ የምንፈልገው ይፈጸማል በሚል ተስፋ መጠባበቅ ግዴታ ሆነባቸው።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ እንዳሰቡትም፤ ከጦርነቱ በኋላ በእንግሊዝ አገር በኮንሴርቫተሮቹ ቦታ ምርጫውን አሸንፎ የተቋቋመው የሌበር የግራ ክንፍ መንግሥት የደጃዝማቹን ጉዳይ ካጠና በኋላ፤ ሰውየው ፍርዱን መቀበል ያለበት በአገሩ ላይ በፈጸመው ክህደት ነው እንጂ፤ የፖለቲካ መልክ የለውም በማለት ውሳኔ ሰጠ። ከፋሽስት ጋር ተዋግተው ኢትዮጵያን ነፃ በማውጣት ባለውለተኞች ናቸው የተባሉት እነ ዊንስተን ቸርችልና እነ አንቶኒ ኤደን በማቅማማት ወይም ለጥናቱ ጊዜ በማጣት ያልፈጸሙትን፤ የሌበር የግራ ክንፍ መንግሥት ይህን ውሳኔ በማድረጉ፤ በአዲስ አበባ የተፈጠረው ደስታ ከፍ ያለ ነበር። የእንግሊዝ መንግሥት ባደረገውም ውሳኔ መሠረት፤ ደጃዝማች ኃይለሥላሴ ጉግሣ እ.ኤ.አ መስከረም 7 ቀን 1946 ዓ.ም በልዩ አውሮፕላን አዲስ አበባ መጠተው የኢትዮጵያ መንግሥት ተረከባቸው።

በመሠረቱ፤ በትግራይና በሸዋ ንጉሣዊ ቤተሰቦች መካከል በጋብቻ መተሳሰር የተጀመረው፤ አፄ ዮሐንስ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥትና አፄ ምኒልክ ንጉሠ ሸዋ ፍቅርን ለማጠንከር ተስማምተው በወሰዱት እርምጃ ነው። የዮሐንስ 4ኛ ወንድ ልጅ ራስ አርዓያ ለምኒልክ ሴት ልጅ ለወይዘሮ ዘውዲቱ (ኋላ ንግሥተ ነገሥታት)

ሲዳሩ፤ የራስ አርዓያ ልጅ የሆኑት ራስ ጉግሣ ደግሞ፤ የአልጋ ወራሽ ተፈሪ መኰንንን የወንድም ልጅ ወይዘሮ የሻሽ ወርቅ ይልማን (ኋላ ልዕልት) አግብተው ነበር። እነዚህ ሁለት ጋብቻዎች በከፍተኛ ደስታና ዝግጅት ከተፈጸሙ በኋላ፤ የወይዘሮ ዘውዲቱ ምኒልክ ባለቤት ራስ አርዓያ በጣም በልጅነት ዕድሜያቸው በድንገት በመሞታቸው፤ ወይዘሮ የሻሽወርቅ ይልማ ደግሞ ከባለቤታቸው ከራስ ጉግሣ ጋር ሳይኳኋኑ ቀርተው በቶሎ በመለያየታቸው፤ ሁለቱም ወገኖች በየበኩላቸው ልጆች ስላልወለዱ፤ ተፈላጊውን ዘር ለማስተሳሰር ሳይቻል ቀረ። ከዚህ ቀጥሎ ግን፤ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት አልጋወራሽ የሆኑት ልዑል መርዕድ አዝማች አስፋወሰን ኃይለሥላሴ ከአፄ ዮሐንስ ቤተሰብ የልዑል ራስ ሥዩም መንገሻን ሴት ልጅ ልዕልት ወለተእሥራኤልን እ.ኢት.አቆ በ1924 ዓ.ም አግብተው አንዲት ሴት ልጅ በመውለዳቸው፤ በታላቁ ቤተመንግሥት ከፍ ያለ የደስታ በዓል ተደርጐ መድፍ ተተኩሷል። በዚያን ጊዜ የተወለዱትም ሴት ልጅ በደርግ ዘመን በእሥር ቤትና በሕመም ተሰቃይተው የሞቱት ልዕልት እጅግአየሁ አስፋወሰን ነበሩ።

## ስለ ደጃዝማች ኃይለሥላሴ ጉግሣ
## Reference


### 1/ NATIONAL ARCHIVES

a. British Delivery of Gougsa To Ethiopia
   884.00/9-1746h
b. Trial of Gougas
   884.00/2-2647
   884.00/4-3047

2/ PUBLIC RECORD OFFICE (U.K)
   FO371 — 27520
   FO371 — 31603

### MEMORANDUM
### REGARDING - HAILE SELASSIE GOUGSA

a. Brigadier, O.E.T.A Eritrea (J.2535) (J.663)
b. Mr. R. Howe From Addis — Ababa
   (J.1605/1134/1)
c. War Cabinet (W.P. (42) 221
   (J.2471)
d. Quai D'Orsay Afrique-Levant
   Nº 428-AL

# ምዕራፍ ፫

## ታዲያስ ! ሊግ ኦፍ ኔሽን ሚናው ምንድን ነው ?

በዤኔቭ የሚገኙት የመንግሥታት ማህበር ድርጅት ኃላፊዎች፣ በኢትዮጵያና በጣልያን መካከል ጥቅምት 3 ቀን 1935 ዓ.ም ጦርነቱን የከፈተው የፋሽስት መንግሥት መሆኑ ባያጠራጥርም፣ በደንቡ መሠረት ጉዳዩ በኮሚቴ ተመርምሮ ሕገ ወጡ ማን እንደሆነ መረጋገጥ አለበት የሚል አቋም ያዙ። ከዚህ በፊት፣ በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል የደረሰውን ጠብ በዝርዝር አጥንቶ የሰላም መፍትሔ እንዲያቀርብ፣ መስከረም 14 ቀን 1935 ዓ.ም የሊግ ኦፍ ኔሽን ምክር ቤት አሥራ ሦስት አባላት ያሉበት ኮሚቴ አቋቁሞ ነበር። ይህ ኮሚቴ እንደተጠበቀው ሥራውን አጠናቅቆ በፍጥነት ለማቅረብ ሳይችል ስለዘገየ፣ ረቡዕ ጥቅምት 3 ቀን ጦርነቱን የከፈተው አጥቂው መንግሥት ማን መሆኑን ለማወቅ እንዲቻል፣ ስድስት አባል አገሮች ያሉበት ሌላ ልዩ ኮሚቴ ጥቅምት 5 ቀን 1935 ዓ.ም ተቋቋመ።

ይህ የስድስቱ አባላት ኮሚቴ ሥራውን ከጀመረ ከዐርባ ስምንት ሰዓቶች በኋላ፣ ለሊግ ኦፍ ኔሽን ምክር ቤት ባቀረበው ራፖር፣ ጦርነቱን በሁለት ግንባር በኤርትራና በሱማሌ በኩል የከፈተው የጣልያን መንግሥት መሆኑን አረጋገጠ። ወዲያውም ቀደም ሲል በመስከረም 14 ቀን የተሠየመው የአሥራ ሦስቱ አባላት ኮሚቴ ለሦስት ሳምንታት ባደረገው ጥናት፣ ከወልወል ግጭት ጀምሮ የጣልያን መንግሥት ኢትዮጵያን በጦር ኃይል ይዞ ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ ቆርጦ መነሣቱንና ለዚህም ግብ በየጊዜው የወሰዳቸውን እርምጃዎች በመተንተን ሪፖርቱን ለሊግ ኦፍ ኔሽን ምክር ቤት አቀረበ። የእነዚህም ፍሬ ነገሮች የሚከተሉት ናቸው።

1. የጣልያን መንግሥት መሪ ሲኞር ሙሶሊኒ የወልወል ግጭት ከደረሰበት ከታህሣሥ 1934 ዓ.ም ጀምሮ፣ ኢትዮጵያ ከዐርባ ዓመታት በፊት በአድዋ ላይ ያደረሰችውን ውርደት ለመበቀልና አገሪቱን በጦር ኃይል ወግቶ ቅኚ ግዛቱ ለማድረግ ያለውን የተቆረጠ ውሳኔ፣ የጣልያን ሕዝብ እንዲያውቀው ከማድረግ አላቋረጠም።

2. በ1923 ዓ.ም ኢትዮጵያ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል እንድትሆን በተወሰነ ጊዜ፣ አገሪቱን ከፊውዳል አስተዳደር ለማላቀቅና ሕጋዊ የሆነ መንግሥት ለመመሥረት የገቡትን ቃል ባለመፈጸማቸው፣ ለአውሮፓ መንግሥታትና በተለይም ለጣልያን ሰላምና ፀጥታ እንቅፋት ሆነዋል። ስለዚህም፣ ኢትዮጵያ ከመንግሥታት ማህበር አባልነቷ እንድትወገድ ያስፈልጋል ሲል፣ የጣልያን መንግሥት በዝርዝር ያቀረበውን ክስ የአሥራ ሦስቱ አባላት ኮሚቴ በጥንቃቄ ተመልክቶታል። ኮሚቴው ባደረገው ምርምር ኢትዮጵያ ለአውሮፓ መንግሥታትና በተለይም ለጣልያን፣ የሰላምና የፀጥታ እንቅፋት መሆኗን የሚያመለክት መረጃ አላገኘም። ይልቁንም የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ከጣልያንና ከሌሎቹም የአውሮፓ አገሮች ጋር

የወዳጅነት ግንኙነት በማስፋፋት፣ የመንግሥታቸውን አስተዳደር ለማሻሻል እስከዛሬ ያደረጓቸው ጥረቶች ሁሉ ሲመረመሩ፣ የሚመስገኑ እንጂ፣ የሚወቀሱ ሆነው አይታዩም።

ማርሴል ግሪዮል " Marcel Griaul " የተባለ ፈረንሣይ፣ ስለ ዓለም ብሔሮች ምርምር አድርጐ ከፍ ያለ ዝና ያገኘና በሳይንስ ችሎታው የተመሰከረለት፣ በተጨማሪም በጣልያኖች ዘንድ የታወቀና የተከበረ ስለሆነ፣ የቀረበውን ዶክመንት አጥንቶ ገለልተኛ የሆነ አስተያየት እንዲሰጥበት የኢትዮጵያ መልዕክተኛ ጠይቆ ነበር። በዚህ መሠረት፣ ማርሴል ግሪዮል ጉዳዩን በዝርዝር ካጠና በኋላ፣* « ... የመንግሥታት ማህበር በኢትዮጵያ ጉዳይ በጥልቀት ተነጋግሮ ከአንድ ውሳኔ ላይ ለመድረስ፣ በጣልያን በኩል ተዘጋጅቶ የቀረበው ዶክመንት፣ ሚዛናዊነት የሌለው መሆኑ መታወቅ አለበት። በዚህ አኳኋን፣ ስለ ኢትዮጵያ የውስጥ ጉዳይ፣ የውጭው ዓለም አንድ ዓይነት እርምጃ ከመውሰዱ በፊት፣ ብዙ ጥንቃቄ ማድረግ ያስፈልገዋል ... » ሲል አስተያየቱን መደምደሙን ኮሚቴው መዝግቧል።

3. ከጥቂት ሳምንታት ወዲህ የጣልያን መንግሥት፣ ለሊግ ኦፍ ኔሽንና ለአውሮፓ አገሮች በሚያስተላልፈው መልዕክት፣ ኢትዮጵያ በኤርትራና በሱማሌ ግዛቱ በኩል በጦር ልትወጋኝ በመዘጋጀት ላይ ነች በማለት ሲያስታውቅ፣ ለአገሩ ሕዝብ ደግሞ በሚሰጠው መግለጫ፣ በቅርቡ የፋሽስት ኃይል ኢትዮጵያን ይዞ የአድዋን ቂም ለመበቀልና ቅኝ ግዛቱ አድርጐ ለመግዛት መወሰኑን ይናገራል። እዚህ ላይ እውነቱ የትኛው እንደሆነ መለየት ያስፈልጋል። በኮሚቴው እንደታየው ከሆነ፣ የኢትዮጵያ መንግሥት ጦር አዘጋጅቶ ጣልያንን ለመውጋት የሚያስብም የሚዘጋጅም አይደለም። ንጉሠ ነገሥቱም የሊግ ኦፍ ኔሽንን ሕግ በትክክል የሚያከብሩና በማህበሩም ተግባር ከፍ ያለ ዕምነት ያሳደሩ መሆናቸውን ደጋግመው ስለአረጋገጡ፣ የጣልያንን መንግሥት የሚያሳስበው ነገር አይታይም።

4. <u>በኢትዮጵያ በኩል፣</u> በሁለቱ አገሮች መካከል የወልወል ግጭት ከደረሰበት ጊዜ ጀምሮ፣ በኤርትራና በሱማሌ ወሰን ላይ የጣልያን መንግሥት የሚያዘጋጀው ጦር እየተስፋፋ በመሄዱ፣ ንጉሠ ነገሥቱ ከፍ ያለ ሥጋት ያደረባቸው መሆኑን ለሊግ ኦፍ ኔሽን ደጋግመው አመልክተዋል። ለዚህም እውነተኛውን ሁኔታ ለመረዳት እንዲቻል፣ ሊግ ኦፍ ኔሽን ዳኞች መርጦ ወደ ሥፍራው እንዲልክና እንዲያስመረምር ጠይቀው በወቅቱ መልስ አልተሰጣቸውም። የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ከወልወል ግጭት ጀምሮ ለሊግ ኦፍ ኔሽን በየጊዜው ያቀረቧቸው አቤቱታዎችና የገለጿቸው አስተያየቶች ሁሉ በዝርዝር ሲታዩ፣ ከጣልያን መንግሥት ጋር ከወዳጅነት በስተቀር የጠብ ፍላጐት ስለሌላቸው፣ ለዕርቅ የተጠየቁትን ሁሉ ለመቀበል ፈቃደኛነታቸውን ከማሳየት አልተቆጠቡም። ለምሳሌም ያህል ባለፈው መስከረም ወር መጀመሪያ ሳምንት ላይ፣ በሊግ ኦፍ ኔሽን የተሠየመው የአምስቱ አባላት አስታራቂ ኮሚቴ፣ ኢትዮጵያ ከመንግሥታት ማህበር

* Les Documents-politique 17ème année No 7.Page 117 (Genéve)

ቴክኒካል እርዳታ እየተሰጣት፣ አስተዳደሯን ለማሻሻል እንድትችልና፣ ጣልያንም ከሌሎቹ የአውሮፓ አገሮች ሁሉ ቅድሚያ ተሰጥቷት በአገሪቱ የኤኮኖሚ ልማት ላይ ከፍተኛውን ቦታ እንድታገኝ አጥንቶ ያቀረበውን ሐሳብ፣ ንጉሠ ነገሥቱ ለመፈጸም ወዲያውኑ ሲቀበሉ፣ አልስማማም ብሎ የሰረዘው የጣልያን መንግሥት መሆኑ የሚዘነጋ አይደለም። ከዚህም በፊት በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል አንድ ዓይነት ሰላም ለመፍጠር እንዲቻል፣ በታላላቆቹ መንግሥታት በኩል የተደረጉትን ጥረቶች ሁሉ አልቀበልም ብሎ እስካሁን የቆየው የጣልያን መንግሥት መሆኑን መካድ አይቻልም።

5. <u>በጣልያን በኩል፤</u> መስከረም 22 ቀን 1935 ዓ.ም የመንግሥቱ እንደራሴ ባሮን አሎይዚ ለሊግ ኦፍ ኔሽን ምክር ቤት በሰጠው መግለጫ፣ « ... በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል ላለው ችግር የሊግ ኦፍ ኔሽን ሕገ መንግሥት መፍትሔ የሚያገኝለት አይደለም ... » ሲል የተናገረው ምን ለማለት እንደሆነ በጥንቃቄ መጠናት አለበት። በዚህ አኳኋን፣ የጣልያን መንግሥት ከኢትዮጵያ ጋር ላለው ጠብ መፍትሔ የሚገኘው በመንግሥታት ማህበር በኩል ሳይሆን እሱ ራሱ በሚመስለው መንገድ ነው ብሎ ከወሰነ፣ ሊግ ኦፍ ኔሽን ባለበት ኃላፊነት በአንቀጽ አሥራ ሁለት (12) አሥራ ሦስትና (13) አሥራ አምስት (15) መሠረት፣ አስፈላጊዎቹን እርምጃዎች ለመውሰድ መዘጋጀት ይኖርበታል።

ፍሬ ነገሮቹ ከዚህ በላይ የተገለጹት የአሥራ ሦስቱ አባላት ኮሚቴ ያደረገው ጥናት፣ ጥቅምት 7 ቀን 1935 ዓ.ም ለሊግ ኦፍ ኔሽን ካውንስል በደረሰበት ዕለት፣ ከአራት ቀናት በፊት በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል ጦርነቱን የከፈተው ማን እንደሆነ እንዲለይ የተቋቋመው የስድስቱ አባላት ኮሚቴም ሪፖርቱን አጠናቅቆ አቀረበ። ሊግ ኦፍ ኔሽን እንደጠየቀው፣ በኢትዮጵያና በጣልያን መካከል የተነሣውን ጦርነት ማን እንደጀመረው ለማወቅ፣ የስድስቱ አባላት ኮሚቴ ጊዜ የሚፈጅ ምርምር ማድረግ አላስፈለገውም። ዕድሜ ለዲክታተሩ መንግሥት የፕሮፓጋንዳ ሚኒስቴር፣ የሚያስፈልጉት መረጃዎች ሁሉ በሚገባ ተዘጋጅተው ቀርበውለታል።

ፍጹም በሆነ በዲክታተር አስተዳደር ውስጥ እያንዳንዱ ባለሥልጣን የሚያደርገው ጥረት ሁሉ፣ በተሰጠው የኃላፊነት ድርሻ መሪውን ለማስደሰት እንጂ፣ የአንዱ ሥራ የሌላውን የሚያፈርስ እንዳይሆን ጥንቃቄ አይደረግም። በዚህም መሠረት፣ የዱቼ የውጭ ጉዳይና የፕሮፓጋንዳ ሚኒስትሮች፣ በኢትዮጵያ ጉዳይ በየመስካቸው አድናቆትን ለማትረፍ እንደዚያ ሲሮጡ፣ በዓለም ታዛቢዎች ዘንድ የፋሽስት መንግሥት የማይታመን ቀጣፊ መሆኑን እንደሚያጋልጡ አላሰቡበትም። <u>*በጥቅምት 3 ቀን 1935 ዓ.ም የሙሶሊኒ መንግሥት የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ለሊግ ኦፍ ኔሽንና ለአውሮፓ አገሮች በላከው መልዕክት፣ ኢትዮጵያ በምሥራቅ አፍሪካ በሚገኙት ግዛቶቻችን ላይ አደጋ ለመጣል ወታደሮቿን ስለአሰለፈች፣ በዚያ የሚገኘው የጦር ሠራዊታችን አስፈላጊውን የመከላከያ እርምጃ እንዲወስድ ትዕዛዝ ተሰጥቷል ሲል ማስታወቁ ይታወሳል። ወዲያው ደግሞ፣ የፕሮፓጋንዳው ሚኒስትር ለመላው የጣልያን ሕዝብ በራዲዮና በጋዜጦች ላይ በገለጸው ሰፊ ሐተታ፣ « ... ተወዳጁ መሪያችን ዱቼ ሙሶሊኒ ዕድለኛ ለሆነው ለጣልያን ሕዝብ የተከበረ ታሪኩን ለማደስ በሰጡት ተስፋ መሠረት፣ የዛሬ ዐርባ ዓመታት ኢትዮጵያ ያደረሰችብንን በደል ለመበቀል፣ ዛሬ ጥቅምት 3 ቀን 1935 ዓ.ም ከንጋቱ በአሥራ ሁለት ሰዓት፣ በታማኙ ፋሽስት በጄኔራል ኤሚሊዮ ደ-ቦኖ የሚመራው ጀግናው ሠራዊታችን የኢትዮጵያን ግዛት ጠርምሶ በመግባት፣*</u>

የሙሶሊኒ ወታደሮች ወደ ኢትዮጵያ ሲጓዙ፤ ዱቼ በፈረስ እየጋለበ አሰናበታቸው፤



"አድዋን" በእጁ አድርጓል ... » የሚል መግለጫ እያስተጋባ ለሕዝቡ መጠን የሌለው የደስታ ማዕበል አወረደለት። እንደዚሁም በዚሁ ቀን፣ አሥመራ ላይ የሚገኘው የፋሽስት መንግሥት እንደራሴ ለኤርትራ ሕዝብ በሰጠው መግለጫ፤ መሬታችሁን ለመቀማትና አገልጋዩ እንድትሆኑ ለማስገደድ፣ ተሰናድቶ የመጣባችሁን የኃይለሥላሴን የሸዋ መንግሥት ጦር ለመደምሰስና፣ ወንድማችሁ የሆነውንም የትግራይ ሕዝብ ከወደቀበት አደጋ ለማዳን፣ በዛሬው ዕለት ጀግናው የፋሽስት ሠራዊት የመረብን ወሰን ጥሶ ኢትዮጵያ ገብቷል፣ ሲል አስታወቀ።

እነዚህ መግለጫዎች ከተሰራጩ በኋላ፣ ጥቅምት 5 ቀን 1935 ዓ.ም ታሪካዊው "የኢትዮጵያ አድዋ" በፋሽስት እጅ መውደቁ በትክክል ሲረጋገጥ፣ በመላ ጣልያን በተለይም በሮማ ከተማ የተደረገው ፈንጠዝያ መቼውንም ታይቶ የማይታወቅ ሆነ። በሮማ፣ ክቡር ዱቼ በቬኔሲያ ፓላስ ቢሮው ሰገነት ላይ ሆኖ፣ በዚያ በትልቁ አደባባይ ለተሰበሰበው በብዙ መቶ ሺህ ለሚቆጠረው ሕዝብ ባደረገው የድል መግለጫ፣ « ... የጣልያን ሕዝብ ስማ ! የጣልያን ሕዝብ ደስ ይበልህ ! የምትተማመንበት የፋሽስት ጦር ሠራዊት የዛሬ ዐርባ ዓመታት የደረሰብህን በደል በመበቀል "አድዋን" በእጁ አድርጐ ይዞልሃል። ዛሬ የአድዋን ብድር የመለሰህ ሠራዊት ነገ ደግሞ መላው ኢትዮጵያ የአንተ ግዛት እንዲሆን ያደርግልሃል ... » አለ። የጣልያን ሕዝብ ከዲክታተሩ መሪው እንደተነገረው « ... ለታላቋ ጣልያን የአድዋን ብድር ከመመለስ የበለጠ ደስታ አይኖራትም ... » በማለት ጭፈራውን ቀጠለ። በዚሁ ጊዜ የአገር ውስጥና የአውሮፓ አገሮች፣ በተለይም የጣልያንና የፈረንሣይ የዜና ማሰራጫ ድርጅቶች ባቀረቡት ሰፊ ሐተታ፣ « ... የፋሽስት ጦር በመረብ በኩል የኢትዮጵያን ወሰን ጥሶ ሲገባ፣ የተቃዋሚ ኃይል አልገጠመውም። ሙሶሊኒ እንደፈለገውና እንደተመኘው፣ በጥቂት ሰዓቶች ውስጥ "አድዋን" ይዟል። የዛሬ ዐርባ ዓመታት በክሪስፒ መንግሥት ደካማነት ንጉሥ ምኒልክ በጣልያን ጦር ላይ ያደረሱት የአድዋ የውርደት ታሪክ፣ በዛሬው ድል ተተክቶ ያለፈው ተደምስሷል ... » እያሉ ለዱቼ ያላቸውን አድናቆት አፋፋሙ።

እንግዲህ ! እዚህ ላይ ተመልካች ይፍረድ ! ሊግ ኦፍ ኔሽን በኢትዮጵያና በጣልያን መካከል ጦርነቱን በመክፈት ሕግ የጣሰው መንግሥት ማን እንደሆነ መርምሮ እንዲያቀርብ ያቋቋመው የስድስቱ አባላት ኮሚቴ፣ ምን የተለየ ጥናት ? ምን የተለየ ምርምር ? ማድረግ ያስፈልገዋል ? ... ቀደም ሲል እንደተነገረው፣ የፋሽስት መንግሥት ራሱ ለጥያቄው መልሱን አዘጋጅቶ አቅርቦታል።

የመንግሥታት ማህበር አባል የሆነችውን ነፃ መንግሥት ነፃነቷን ገፍፎ ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ የወሰነ፣ የጦር ዝግጅቱንም አጠናቀቆ ወሰን በመጣስ ጦርነቱን የከፈተ፣ የፋሽስት መንግሥት መሆኑን ራሱ ዱቼ ሙሶሊኒ የሚክደው አልነበረም። ሆኖም፣ እውነተኛውን ጉዳይ አጣርተው እንዲያቀርቡ ሊግ ኦፍ ኔሽን አደራ የጣለባቸው ኮሚቴ ዐሥራ ሦስትና ኮሚቴ ስድስት፣ ለእያንዳንዳቸው በተሰጣቸው መምሪያ መሠረት፣ ትክክለኛውን ሁኔታ ለማስረዳት ችግር አልገጠማቸውም። በኢትዮጵያና በጣልያን መካከል በተነሣው ጠብ፣ በማናቸውም መስክ ሕገ ወጥ ሆኖ የተገኘው የጣልያን መንግሥት እንጂ፣ ኢትዮጵያ ከሰላም ፈላጊነቷ በስተቀር አንዳች እንከን እንዳልተገኘባት፣ ሁለቱም ኮሚቴዎች ራፖራቸውን ጥቅምት 7 ቀን 1935 ዓ.ም ለሊግ ኦፍ ኔሽን ጠቅላላ ጉባኤ አቀረቡ።

# ምዕራፍ ፬

## በግፈኛው መንግሥት ላይ የኤኮኖሚ እገዳ፣ ምን ሊጎዳ ?

በገኔቭ ያሉት የሊግ ኦፍ ኔሽን መሪዎች፣ ምንም እንኳ የሙሶሊኒ ደጋፊዎች ቢሆኑም፣ ጥቅምት 3 ቀን 1935 ዓ.ም ሕግ ጥሶ በኢትዮጵያ ላይ ጦርነት ያነሣው የፋሽስት መንግሥት መሆኑን፣ እነሱ ራሳቸው ባቋቋሙት ኮሚቴ ተረጋግጦ ስለቀረበላቸው፣ በደንቡ መሠረት ተገቢውን እርምጃ ከመውሰድ ለማምለጥ የሚችሉበት መንገድ አላገኙም። ሙሶሊኒም በሚፈጽመው የግፍ ሥራ፣ ሊግ ኦፍ ኔሽን የጠነከረ እርምጃ ቢወስድበት ከባድ ችግር ላይ እንደሚወድቅ ደህና አድርጐ ያውቅ ነበር። ሆኖም፣ ይህ ችግር እንዳይከብድበት በወዳጁ በፈረንሣዩ መሪ በፒየር ላቫልና ከሌሎቹም አንዳንድ አባል መንግሥታት በሚደረግለት እርዳታ ተስፋ ማሳደሩ አልቀረም።

የኢትዮጵያን ግዛት ጥሶ አድዋን በእጁ ማድረጉን ለጣልያን ሕዝብ ባስታወቀበት ጊዜ፣ በገኔቭ ያለው የመንግሥታት ማህበር በእንግሊዞች ቆስቋሽነት አንዳንድ እርምጃዎች በመውሰድ ሊያጠቃው እንደሚችል ያለውን ሥጋት አልደበቀም። በዚህ ጉዳይ ሕዝቡን ለማዘጋጀት ባደረገውም ንግግር፣ « ... የመንግሥታት ማህበር የአድዋን ብድር ለምን መለሳችሁ ? ብሎ ሊያጠቃን ከተነሣ፣ ሁላችንም በአንድነት ሆነን የሚደርስብንን መመከት አለብን። የኢኮኖሚ ጉዳት እንዲደርስብን ቢያውጅብን፣ ቀበቶአችንን አጥብቀን እንቋቋመዋለን። ጦር አዘጋጅቶ ሊወጋን ቢመጣ፣ በጦር ኃይላችን እንገጥመዋለን ... » በማለት በአንድ በኩል ሥጋቱን፣ በሌላ በኩል ፉከራውን በሕዝቡ መንፈስ ላይ ለማሳደር ብዙ ሞክሯል።

በመንግሥታት ማህበር ደንብ በአንቀጽ ዐሥራ ስድስት (16) ላይ እንደሰፈረው፣ አንድ አባል መንግሥት ሌላውን ማህበርተኛ ሕግ ጥሶ በጦር ኃይል ሲወጋው ከተገኘ፣ ጥቃቱ የመላው አባል አገሮች ሆኖ ስለሚቆጠር፣ ሁሉም በአንድነት ሆነው በሕገ ወጡ መንግሥት ላይ እርምጃ መውሰድ ይጠበቅባቸዋል። ይህም እርምጃ፣ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል የሆኑት አገሮች ሁሉ፣ ከሕገ ወጡ መንግሥት ጋር ያላቸውን የኢኮኖሚ፣ የንግድና የፊናንስ ግንኙነታቸውን በሙሉ በማቋረጥ ከፍ ያለ ጉዳት እንዲደርስበት የሚያደርግ ነው። ሙሶሊኒም የፈራው፣ በሊግ ኦፍ ኔሽን ሕግ አንቀጽ ዐሥራ ስድስት መሠረት፣ አባል መንግሥታት ሁሉ ሳይለያዩ በአንድነት ሆነው በጣልያን ላይ የጠነከረ የኢኮኖሚ እገዳ ካደረጉ፣ የፋሽስት መንግሥት ብርቱ አደጋ ላይ እንደሚወድቅ ስለተረዳው ነው። ለምሳሌ፣ ጣልያን ለሕይወቷ መተዳደሪያ ከልዩ ልዩ አገሮች ከምታስመጣቸው ጥሬ ዕቃዎች ሌላ፣ በተለይ የነዳጅ ዘይት ከማግኘት ብትታገድ፣ ሌላው ቀርቶ መላ ኢትዮጵያን ለመውረር የተሰማራው ጦር ከሁለት ወር የበለጠ መጠባበቂያ (ሪዘርቭ) ስለሌለው፣ ሚሲዮኑን ሳይፈጽም ማሕል መንገድ ላይ ድል ሆኖ ሊበተን ይችላል። በዚህ ጉዳይ ሲኞር ዱቼ ለወዳጁ ለፈረንሣይ ጠቅላይ ሚኒስትር ለፒየር ላቫል በላከው ልዩ መልዕክት፣ « ... የመንግሥታት ማህበር በአገሬ ላይ የኢኮኖሚ እገዳ

እንደሚያውቁ አውቃለሁ። ሆኖም ይህ እገዳ የነዳጅ ዘይት እንዳላገኝ የሚያስደርግ ከሆነ፣ በኢትዮጵያ ላይ የጀመርኩትን ዘመቻ እንደሚያቋርጥብኝ ሥጋቴን ልገልጽልዎ እወዳለሁ። በተጨማሪም የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት፣ በተቃዋሚያችን በአንቶኒ ኤደን አነሣሽነት፣ ምናልባት የጣልያን መርከቦች በስዊዝ ካናል እንዳይተላለፉ እገዳ ለማድረግ ያስብ ይሆናል፣ የሚል ጥርጣሬ አለኝ። ይህ ደግሞ ሌላ ተጨማሪ ችግር ነው። ሆኖም እርስዎን የመሰለ ወዳጅ ስላለን፣ የምንሠጋባቸውን ጉዳዮች ሁሉ የፈረንሣይ ድምፅና ኃይል ይገታልናል ብለን ተስፋ እናደርጋለን ... » ሲል ማሳሰቢያውን አጠነከረ። ላቫልም ሳይውል ሳያድር በሰጠው መልስ፣ « ... እርስዎ በአገርዎ ስም የሚያስቡትን ሁሉ በተግባር የሚገልጹ ባለሙሉ ሥልጣን የመንግሥት መሪ ነዎት። እኔ ግን በፓርላማ ክብዙ የፖለቲካ ፓርቲዎች ጋር እየተሟገትኩ በድምፅ ብልጫ የምሠራ መሆኔን አይዘንጉት ! ሆኖም በገነባነው ወዳጅነት ተመሥርቼ፣ ለርስዎ የምችለውን ሁሉ ከማድረግ እንደማልቆጠብ ይመኑኝ ! ... » በሚል ቃል፣ ዱቼ ችግሩን እንዲያውቅለት ሞክሮ ነበር። ሙሶሊኒ ግን፣ ይህን እየተደጋገመ የሚቀርብለትን የላቫልን የልመና ጸሎት መስማት ስለሰለቸው አያዳምጠውም። ዲክታተሩ፣ በዴሞክራሲ ሥርዓት በፓርላማ የሚከናወን የፖለቲካ ፓርቲዎች ቁጥጥር ስለሌለበት፣ የፈረንሣይ ጠቅላይ ሚኒስትር እንደ እሱ ባለሙሉ ሥልጣን ሆኖ የሚሠራ ይመስለዋል። ፒየር ላቫል በኢትዮጵያ ጉዳይ ሙሶሊኒን ለመርዳት እርምጃ የወሰደው፣ የፋሽስቱን መንግሥት ወዳጅ አድርጐ መያዝ ለፈረንሣይ ከፍ ያለ ጥቅም ያስገኝላታል በማለት ፓርላማውን እያጭበረበረ ነው እንጂ፣ እሱ ብቻውን የፈለገውን ለማድረግ የሚያስችል ሥልጣን ኖሮት አይደለም። ይህም ጉዳይ ወደፊት የበለጠ እየተጋለጠ ይታያል።

ዓርብ ጥቅምት 11 ቀን 1935 ዓ.ም በተደረገው የሊግ ኦፍ ኔሽን ጠቅላላ ጉባኤ ላይ፣ ዋናው የመነጋገሪያ አጀንዳ የጣልያንና የኢትዮጵያ ጦርነት ጉዳይ ስለሆነ፣ የየመንግሥታቱ እንደራሴዎች አቋማቸውን የሚገልጹበትና በመጨረሻም አንድ ውሳኔ የሚሰጥበት ዕለት ነበር። በዚህ ዕለት በተደረገው ስብሰባ ላይ የተገኙት የሃምሳዎቹ መንግሥታት እንደራሴዎች ሁሉ (ከጣልያን በስተቀር) የሙሶሊኒ ጦር ኢትዮጵያን በመውረር ላይ የሚገኝ መሆኑን በሚገባ የተረዱት ስለሆነ፣ የፋሽስቱን መንግሥት በአንድ ድምፅ ለማውገዝ አልተቸገሩም። ይሁን እንጂ፣ ዋናው ቁም ነገር ሙሶሊኒን ማውገዝ ብቻ ሳይሆን፣ በሕገ መንግሥቱ አንቀጽ 16 መሠረት፣ ኢትዮጵያን ለማዳን፣ ሊግ ኦፍ ኔሽን አስፈላጊውን እርምጃ እንዲወስድና ኃላፊነቱን እንዲፈጽም ውሳኔ መስጠት ነበር። ምን ዓይነት እርምጃ ? ... ምንም እንኳ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት አድሮበት እንደነበረው ተስፋ፣ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል አገሮች ተባብረው ግፈኛውን የፋሽስት መንግሥት በጦር ኃይል ለመውጋት የሚነሡ ባይሆኑም፣ በጣልያን ላይ ከፍ ያለ የኢኮኖሚ ጥቃት በማድረስ፣ የኢትዮጵያን ነፃነት ለማስከበር የሚያስችል አቅም እንደሚኖራቸው የታወቀ ነበር። በዚህም መሠረት፣ የታላቋ ብሪታንያ መልዕክተኛ አንቶኒ ኤደንና የመስኮቡ ዋና ወኪል ሊትቪኖቭ (Litvinov) እንዲሁም የሩማንያው ሚኒስትር ቲቱሌስኮ (Titulesco) አንድ ግንባር ይዘው፣ የመንግሥታት ማህበር ጠቅላላ ጉባኤ አንቀጽ ዐሥራ ስድስትን በመመርኮዝ፣ በሙሶሊኒ መንግሥት ላይ መውሰድ ያለበትን የኢኮኖሚ እገዳ በአስቸኳይ እንዲወስን ጠየቁ።

በእነ አንቶኒ ኤደን አስተያየት፣ የሙሶሊኒ መንግሥት በአንቀጽ ዐሥራ ስድስት መሠረት በሚወሰድበት እርምጃ፣ አገሩ የሚያመርተውን ሁሉ ወደ ውጭ ለመሸጥ ስለሚከለከልና፣ ከውጭ የሚያስፈልገውንም ሁሉ ለመግዛት እንዳይችል

ስለሚታገድ፣ በጥቂት ጊዜያት ውስጥ ኢኮኖሚው ወድቆ ከባድ ችግር ይደርስበታል። በዚህም ጊዜ ሙሶሊኒ በኢትዮጵያ ላይ የጀመረውን ጦርነት ከማቆምና የሰላም ንግግር ከማድረግ በስተቀር ሌላ ምርጫ አይኖረውም፣ የሚል ነበር። በዚህ ከጥቅምት 11 ቀን 1935 ዓ.ም ጀምሮ በተደረገው የሊግ ኦፍ ኔሽን ጠቅላላ ጉባኤ ላይ፣ ከአንዳንድ መልክተኞች የተሰጠውን አስተያየት መመልከት አስፈላጊ ይሆናል።

## አንቶኒ ኤደን የታላቋ ብሪታንያ ዋና መልዕክተኛ፣

« ... ሊግ ኦፍ ኔሽን የተመሠረተበትን ዓላማ መፈጸም ወይም አለመፈጸሙ የሚታይበትና የሚፈረድበት፣ ይህን ጦርነት ለማቆም የማይችል ሆኖ ሲገኝ ነው ... »

« ... የግርማዊ የእንግሊዝ ንጉሥ መንግሥት የሚከተለው የውጭ ጉዳይ ፖሊሲ፣ በሊግ ኦፍ ኔሽን አቋምና ተግባር ላይ የተመሠረተበት ምክንያት፣ የዓለምን ሰላምና የሕዝቦችን ደህንነት ለመጠበቅ፣ ከዚህ የተሻለ መንገድ አለመኖሩን በማመን ነው። ... ጦርነት እጅግ የሚያስከፋና አሰቃቂ ነገር ስለሆነ፣ የዓለምን ሕዝብ ከዚህ ክፉ አደጋ ለማዳን ይበጃል ብለን የመሠረትነው የሊግ ኦፍ ኔሽን ሕግ፣ በተግባር ላይ እንዲውል ግዴታው የሁላችንም መሆኑን ማመን አለብን። በዚህ አኳኋን፣ የመንግሥታት ማህበራችን ሁለት ዓይነት የተግባር አፈጻጸም ሥርዓቶች አሉት። የመጀመሪያው፣ በአገሮች መካከል የሚፈጠረው አለመግባባት ወደ ጦርነት እንዳያመራ መፍትሔውን በሰላም ጉዳና ማግኘት ነው። ይህ የማይሳካ ከሆነ ደግሞ፣ ቀጥሎ ያለብን ብርቱ ኃላፊነት ጦርነቱን በግዴታ የማቆም ተግባር ይሆናል። ... በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል በተፈጠረው ጠብ፣ ጦርነት እንዳይነሣ በመንግሥታት ማህበር ዓላማ መሠረት ያደረግነው ጥረት ሁሉ ሳይሳካልን በመቅረቱ፣ ከፍላጐታችን ውጭ በሆነ መንገድ ውጊያው ተጀምሯል። በመጨረሻው ደረጃ አሁን ያለብን ኃላፊነት፣ ይህን የተጀመረውን አሳዛኝ ጦርነት፣ የመንግሥታት መህበርን ሕግ ተመርኩዘን እንዲቆም ማድረግ ነው። ሊግ ኦፍ ኔሽን የተመሠረተበትን ዓላማ መፈጸሙ ወይም አለመፈጸሙ የሚታይበትና የሚፈረድበት፣ ይህን ጦርነት ለማቆም የማይችል ሆኖ ሲገኝ ነው። ስለዚህም፣ ሊግ ኦፍ ኔሽን ያለበትን ግዴታ በተግባር ለማዋል፣ ሁላችንም ሐሳባችንን ማስተባበርና ተገቢውን እርምጃ በፍጥነት መውሰድ ይኖርብናል። ... እኔ በግርማዊ የታላቋ ብሪታንያ ንጉሥ መንግሥት ስም ሆኜ፣ በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል የተነሣውን ጦርነት ለማቆም ፣ ሊግ ኦፍ ኔሽን በሚወስደው እርምጃ ድርሻዬን ለመፈጸም ዝግጁ መሆኔን አረጋግጣለሁ... »

## ሚስተር ፖተምኪን፣ የመስኮብ ዋና መልዕክተኛ፣

« ... ሕጉን ተመርኩዘን የኢትዮጵያን ነፃነት ለማስከበር ካልቻልን፣ በማህበራችን ሕይወት ላይ መፍረዳችንን ማወቅ አለብን ... »

‹‹ … የሶቪየት ሕብረት መንግሥት የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል ለመሆን የወሰነው፤ ማህበሩ የተመሠረተበት ዓላማ ለዓለም ሰላምና ለሕዝቦች ደህንነት አስፈላጊውን ዋስትና ይሰጣል በሚል ዕምነት ነው። በአሁኑ ሰዓት እኛ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባሎች የሆንነው አገሮች ሁሉ፤ በጥልቅ ልንገነዘበው የሚገባው፤ **ከመካከላችን አንዱ አባል መንግሥት ሕግ ጥሶ የሌላውን ማህበርተኛ ነፃነት ለመግፈፍና ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ በጦር ኃይል በማጥቃት ላይ የሚገኝ መሆኑን ነው።** አንድ አባል መንግሥት በሌላው ላይ የሚያደርገው ይህን የመሰለው አሳዛኝ ሕገ ወጥ ሥራ፤ የሊግ ኦፍ ኔሽንን መሠረታዊ አቋም የሚጻረር ስለሆነ፤ ፈጣን እርምጃ በመውሰድ ግዳጃችንን መፈጸም ይኖርብናል። **ደዌ በሰው ላይ አመርቅዞ ክፉ አደጋ ሊያደርስ የሚችለው፤ ገና ከመጀመሪያው ፍቱን መድኃኒት ሳይገኝለት ሲቀር ነው።** እንደዚሁም የመንግሥታት ማህበራችን ዛሬ የተደቀነበት አደጋ እየተስፋፋ ለዓለም ሰላም ጠንቅ ከመሆኑና እሱም ራሱ ፈርሶ ከመጥፋቱ በፊት፤ በሕጋችን መሠረት ተገቢውን እርምጃ ከመውሰድ ማቅማማት የለብንም። **በዚህ ጉዳይ አንድነታችንን አጠንክረን፤ ሕጉን ተመርኩዘን፤ የኢትዮጵያን ነፃነት ለማስከበር ካልቻልን በማህበራችን ሕይወት ላይ መፍረዳችንን ማወቅ አለብን …** ››

## ዤኔራል ነሙር፤ የሐይቲ መልዕክተኛ፤

**‹‹ … እኛ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባሎች፤**
**ትልልቆች ሆንን ትንንሾች፤**
**ሀብታሞች ሆንን ድሆች፤**
**ኃይለኞች ሆንን ደካሞች፤**
**ነጮች ሆንን ጥቁሮች፤**
**ፍርዳችን ከተዛባ፤ አንድ ቀን የኢትዮጵያ ዕጣ**
**እንደሚደርስብን ማመን አለብን … ››**

‹‹ … በዛሬው ዕለት፤ ሊግ ኦፍ ኔሽን በሁለት አባል አገሮች መካከል ስለተነሣው ጦርነት ለሚሰጠው ፍርድ፤ የሐይቲ ሬፑብሊክ መንግሥት የራሱን የኃላፊነት ድርሻ በትክክል ከመፈጸም የሚያመነታ አለመሆኑ እንዲታወቅለት እፈልጋለሁ።

… **ሊግ ኦፍ ኔሽን የገጠመው የፍርድ ጥያቄ፤ የተለየ ምርምር የሚያስፈልገው አይደለም።** ይኸውም፤ በአንድ በኩል የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል የሆነ መንግሥት ኃይልን ተመርኩዞ የሌላውን ማህበርተኛ መንግሥት ነፃነቱን ለመግፈፍና ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ ጦርነት የከፈተ ሲሆን፤ በሌላ በኩል ደግሞ ግፉ የደረሰበት ተጠቂው አገር በሕጉ መሠረት፤ መብቱና ነፃነቱ እንዲጠበቅለት በወግ የጠየቀ ነው። እንግዲህ ! እዚህ ላይ የማህበራችንን ሕግ ጥሶ ግፍ በሚፈጽመውና ጥቃቱ ደርሶበት አቤቱታውን ባቀረበው ማህበርተኛ መካከል፤ ወንጀለኛው ማን እንደሆነ ለይቶ ተገቢውን ፍርድ ለመስጠት ምን ችግር ይኖራል ? ከዚህስ የተሻለ ለውሳኔ ምቹ የሆነ ጉዳይ የት ይገኛል ? … **በዚህ አኳኋን የፋሽስቱ ኮሎኒያሊስት መንግሥት በአንድ አባል በሆነ አገር ላይ በጀመረው ጦርነት ድልን አግኝቶ እስኪጨፍርብን እንጠብቃለን ? ወይስ ግፍ ለደረሰበት ማህበርተኛችን ፈጣን እርምጃ ወስደን የነፃነት መብቱን እናስከብራለን ?** … ለዚህ ጉዳይ ዛሬ የምንሰጠው መልስና የምናደርገው ውሳኔ፤ ጠቃሚ መሆን የሚችለውና በታሪክ ላይ የሚመዘገበው፤ ለአፍሪካ ብቻ ሳይሆን ለነገውም አውሮፓ ነው። ዛሬ በአንድ

አፍሪካዊ አገር ላይ የደረሰው አደጋ፣ ነገ በሌላው አውሮፓዊ አገር ላይ የማይደርስበት ምክንያት የለም። እንደሚታወቀው፣ በሊግ ኦፍ ኔሽን መሠረታዊ ደንብ፣ ለድሆች አፍሪካውያኖችና ለባለጸጐች አውሮፓውያኖች ተለያይቶ የቆመ ሕግ የለም። ኃይለኛው ደካማውን እንዳያጠቃ፣ የአገሮች ነፃነትና የሕዝቦች መብት በእኩል ደረጃ እንዲከበር፣ ለሊግ ኦፍ ኔሽን የተሰጠው ኃላፊነትና የተደነገገው ሕግ፣ ለአውሮፓ ወይም ለአፍሪካ፣ ለእስያ ወይም ለአሜሪካ ተብሎ አልተዘረዘረም። ሕጉ የተሠራው፣ በዓለም ላይ ነፃነታቸው ታውቆላቸው የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል ለሆኑት ነፃ አገሮች በሙሉ መሆኑን የሚክድ የለም።

- እንደዚሁም፣ ዛሬ በጦርነት እሳት ውስጥ የሚገኙት ጣልያንና ኢትዮጵያ፣ በእኩል ደረጃ የሊግ ኦፍ ኔሽን ሕጋዊ አባሎች ለመሆናቸው ጥያቄ አይቀርብበትም።
- እንደዚሁም፣ ፋሽስቱ የጣልያን መንግሥት፣ ኢትዮጵያ ከአውሮፓ ሥልጣኔ ወደ ኋላ የቀረች በመሆኗ፣ በቅኝ ግዛት ላስተዳድራት ይገባኛል ብሎ ጦርነት የከፈተባት መሆኑን፣ መላው የጣልያን ሕዝብ መመስከር ስለሚችል፣ ለሊግ ኦፍ ኔሽን የተለየ ማስረጃ እንዲቀርብለት አያስፈልግም።
- እንደዚሁም፣ የኢትዮጵያ የምዕራብ ሥልጣኔን መከተል ወይም አለመከተል፣ የፋሽስቱን መንግሥት የሚመለከተው ካለመሆኑም በላይ፣ ይህች አገር ከጣልያን ሕዝብ በፊት ወንጌልን የተቀበለች፣ የራሷ የሆነ ጥንታዊ ሥልጣኔና የተከበረ የብዙ ሺህ ዓመታት ታሪክ ያላት መሆኑን መዘንጋት አይቻልም።
- እንደዚሁም፣ የፋሽስቱ መንግሥት በሰላማዊው የኢትዮጵያ ሕዝብ ላይ፣ የጫረውን ሕገ ወጥ የሆነ የጦርነት እሳት ለማቆም፣ ሊግ ኦፍ ኔሽን የሚሰጠው ፍርድና የሚወስደው እርምጃ ምን መሆኑን ለማየትና ለመታዘብ፣ የዓለም ሕዝብ ፊቱን ወደ ዤኔቭ መልሶ አሰፍስፎ የሚጠባበቅ መሆኑን እያወቅን ችላ ማለት የለብንም።

... እኔ ይህን ሁሉ ስናገር፣ ለአንዳንዶቻችሁ ንግግሬ በመርዘሙ ምን ያህል እንደሰለቻችሁ፣ የምገልጸውም ሐሳብ ምን ያህል እንዳልጣማችሁ ሳልገነዘብ ቀርቼ አይደለም። የእኔ የአንዲት "ሐይቲ" የተባለች የጥቁር ሕዝቦች ድሀ አገር ወኪል፣ በኢትዮጵያ ላይ የደረሰው አሳዛኝ በደል ትክክለኛ ፍርድ እንዲሰጠው፣ መላውን የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል አገሮችን፣ ለማሳሰብና ለመማፀን ሐሳቤን ዘርዝሬ ከመናገር በስተቀር፣ ሌላ ምንም ዓይነት ጥቅም ስለሌለኝ መሆኑን እንድትረዱልኝ እጠይቃለሁ።

በንግግሬም መጨረሻ ላይ እንድታዳምጡኝ አጥብቄ እምለምናችሁ፣ በዚህ በምንኖርበት ዓለምና በዚህ ተስፋ በጣልንበት ማህበራችን ውስጥ፣ ዛሬ በሁለት አገሮች መካከል የደረሰውን ጠብ የምንመለከተውና የምንወስነው፣ ጥልቅ በሆነ መንፈስና ሰብዓዊነትን በተመረኮዘ ፍርድ እንዲሆን ነው።

... እኛ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባሎች ሆነን የዳኝነት ወንበር የያዝን አገሮች ሁሉ፣ የምንሰጠው ፍርድ ተዛብቶ ግፈኛውን ለመርዳት የሚያዘነብል ሆኖ

ከተገኘ፣ ትልልቆች ሆነን ትንንሾች፣ ሀብታሞች ሆነን ድሆች፣ ኃይለኞች ሆነን ደካሞች፣ ጥቁሮች ሆነን ነጮች፣ አንድ ቀን የኢትዮጵያ ዕጣ እንደሚደርሰን ማመን አለብን … »

ከዚህ በላይ እንደታየው፣ እነዚህ የታላቋ ብሪታንያ፣ የመስኮብና የሐይቲ መልዕክተኞች፣ እያንዳንዳቸው ለጉባኤው ባሰሙት ሰፊ ንግግር፣ የፋሽስት መንግሥት በኢትዮጵያ ላይ የሚፈጽመው ግፍ ምን ያህል እንዳሳዘናቸው ጥልቅ ስሜታቸውን ከመግለጻቸው በላይ፣ ሊግ ኦፍ ኔሽን የሚወስደው እርምጃ የተፋጠነ እንዲሆን የጠበቀ ማሳሰቢያ ሰጥተዋል። ከእነዚህ ከሦስቱ አገሮች መልዕክተኞች ጋር ሌሎቹም የዐርባ ሰባት መንግሥታት እንደራሴዎች ተመሳሳይ በሆነ አቀራረብና አገላለጽ፣ የፋሽስት መንግሥት የሊግ ኦፍ ኔሽንን ሕግ ጥሶ በኢትዮጵያ ላይ ጦርነት ማንሣቱ፣ በኮሚቴ ስድስት ተመርምሮ የተረጋገጠ ስለሆነ፣ የሊጉ ሕግ አንቀጽ አሥራ ስድስት (16) በሚያዘው መሠረት፣ አስፈላጊው እርምጃ እንዲወሰድ ጠየቁ። ወዲያውም፣ በእንግሊዙ ዋና መልዕክተኛ በአንቶኒ ኤደን ግንባር ቀደምትነት የመስኮቡ ሊትቪኖቭና የሩማኒያው ቲቱሌስኮ ተባብረው ባደረጉት ብርቱ ጥረት፣ ለጠቅላላው ጉባኤ ከተሰበሰቡት ከሃምሳ አራቱ የመንግሥታት እንደራሴዎች መካከል፣ የሃምሳዎቹን ድጋፍ ለማስገኘት በመቻላቸው፣ በጣልያን ላይ የሚፈረደው የኤኮኖሚ ዕገዳ በከፍተኛ የድምፅ ብልጫ እንዲፀድቅ አስደረጉ። ይህንን ውሳኔ አልቀበልም በማለት የተቃወመው የሙሶሊኒ መንግሥት ብቻ ሲሆን፣ የተቀሩት ሦስቱ አገሮች፣ ኦስትሪያ፣ ሐንጋሪና፣ አልባኒያ ድምጻቸውን ያልሰጡት፣ ከፋሽስቱ መንግሥት ጋር ባላቸው የተሳሰረ ግንኙነት ምክንያት መሆኑን አስረድተዋል።

የሊግ ኦፍ ኔሽን ጠቅላላ ጉባኤ ይህን ውሳኔ ካጸደቀ በኋላ፣ የሚደረጉት የኤኮኖሚ እገዳዎች ምንና ምን መሆናቸውን ለይቶ የሚዘረዝር፣ አሥራ ስምንት አባል አገሮች የሚገኙበት ኮሚቴ ተቋቋመ። ኮሚቴ አሥራ ስምንት በየዕለቱ እየተሰበሰበ ሥራውን በሚያከናውንበት ጊዜ፣ የሲኞር ሙሶሊኒ ወዳጆች እነ ፒየር ላቫል፣ የኤኮኖሚው እገዳው በቶሎ በተግባር እንዳይውል ለማዘግየት፣ የማሰናከያ ተንኮል መተብተብ ጀመሩ። ይኸውም፣ የኤኮኖሚውን እገዳ በፍጥነት ከማሳወጅ በፊት፣ ኢትዮጵያንና ጣልያንን የሚያስማማ አንድ ዓይነት የዕርቅ ሐሳብ ለማግኘት መሞከር ይገባናል የሚል ነው። አንቶኒ ኤደን በዚህ ሐሳብ አለመስማማቱን ወዲያውኑ አስታወቀ። የላቫል ሐሳብ ግቡ ምን እንደሆነ ለመገንዘብ ምሥጢሩ የተሸፈነ አልነበረም። የኤኮኖሚው እገዳ ዝርዝሩ ተዘጋጅቶ ከመታወጁ በፊት ጥቂት ቀናት ቢዘገይ፣ ዱቼ ባለው ከፍተኛ የጦር ኃይል መላዋን ኢትዮጵያን ለመያዝ ጊዜ ስለሚያገኝ፣ ከብዙ ጉዳት ሊድን ይችላል፣ በሚል ዓላማ መሆኑን ኤደንና ቲቱሌስኮ ተገንዝበዋል። በመሠረቱ ሙሶሊኒም የሚመኘው ይህንኑ ነበር። በዚያች ሰዓት ለኢትዮጵያ ዋና ተሟጋች መሆኑ የታወቀለት የእንግሊዙ ሚኒስትር አንቶኒ ኤደን፣ ከመስኮብና ከሩማንያ፣ እንዲሁም ከካናዳና ከሜክሲኮ መልዕክተኞች ጋር ሆኖ የላቫልን ሐሳብ በመቃወም፣ ኮሚቴ አሥራ ስምንት ሥራውን እንዲያፋጥን ጠየቀ። ለላቫልም በሰጠው መልስ፣ « … ኢትዮጵያንና ጣልያንን የሚያስማማ የተረጋገጠ አስታራቂ ሐሳብ አለኝ ካልክ፣ ተነጋግረንበት ወዲያውኑ የኤኮኖሚውን እገዳ ለመሰረዝ የሚያዳግት ነገር የለም … » አለው።

ፒየር ላቫል በየጊዜው በሚሰጠው መግለጫ ሁሉ፤ የሊግ ኦፍ ኔሽን ዓላማና ሕግ እንዲከበር ፈረንሣይ አጥብቃ ትደግፋለች እያለ ደጋግሞ ቢናገርም፤ በጣልያንና በኢትዮጵያ መካከል ላለው ጠብ መፍትሔ የሚፈልገው፤ ሙሶሊኒን በሚጠቅም መንገድ ብቻ መሆኑን፤ የገኔቭ መልዕክተኞች በሙሉ ተረድተውታል። ላቫል እውነተኛውን ሐሳቡን ደፍሮ በግልጽ ባይናገረውም ዳር ዳሩን የሚያንዣብበው፤ ዱቼ ሙሶሊኒ በሊግ ኦፍ ኔሽን ስም ኢትዮጵያን አሠልጥን ተብሎ ስጦታ እንዲደረግለት ነበር። በተለይ የፈረንሣይ ጠቅላይ ሚኒስትርና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ከሆነበት ከሰኔ ወር 1935 ዓ.ም ጀምሮ፤ በየጊዜው በገኔቭ ትሪቡን ላይ እየወጣ ስለ ኢትዮጵያ ጉዳይ ሲናገር፤ « ... ለዓለም መንግሥታት የሰላም ዋስትና እንዲሰጥ የቆመው የሊግ ኦፍ ኔሽን ሕግ በትክክል እንዲከበር ያስፈልጋል ... » በማለት ላቫል የሚፎክረው፤ ውስጣዊ ስሜቱና በጀርባ ሆኖ መሥራት የሚፈልገው ምን እንደሆነ እንዳይታወቅበት ለመሸፋፈን መሆኑ ተደርሶበታል። ጥር 7 ቀን 1935 ዓ.ም ሮም ሔዶ ከሙሶሊኒ ጋር በተዋዋለው ስምምነት፤ የፋሽስት ጦር ኢትዮጵያን ለመውረር በሚያደርገው ዘመቻ፤ ዱቼን " ነፃ እጅ አለህ " (Main Libre) ብሎ፤ በፈረንሣይ ስም ሆኖ የሰጠው ቃል፤ ከምሥጢሩ ማህደር ሳይወጣ ተሸፍኖ የሚቀር መስሎት ነበር። ዲክታተሩም ፋሽስት፤ በዚህ ስምምነት ከፈረንሣይ የተሰጠው እርዳታ እጅግ አድርጐ ስለአስደሰተውና ስለ አስተማመነው፤ የታላቋ ብሪታንያን መንግሥትና በተለይም የሊግ ኦፍ ኔሽን ጉዳይ ሚኒስትሩን አንቶኒ ኤደንን እየነቀፈ፤ በኢትዮጵያ ላይ ጦርነቱን ማካሔድ ጀመረ።

የመንግሥታት ማህበር ዋና ጸሐፊ የሆነው ፈረንሣዩ ዮሴፍ አቬኖል፤ ተደጋግሞ እንደተገለጸው፤ የዱቼ ሙሶሊኒ አድናቂና ወዳጅ ስለሆነ፤ ከላቫል ጋር በመተባበር የኢትዮጵያ ጉዳይ ለምክር ቤቱ በቶሎ ቀርቦ ሳይታይ እንዲዘገይ ለማድረግ ከልቡ ፈልጐ ነበር። ነገር ግን፤ የእንግሊዝና የመስኮብ መልዕክተኞች እየተከታተሉ ስለአስጨነቁት በማህበሩ ደንብ መሠረት፤ ጦርነቱን የጀመረው ሕገ ወጥ ማን መሆኑ በኮሚቴ ተጠንቶ እንዲታወቅና ከዚያም ለጠቅላላው ጉባኤ ቀርቦ እንዲወሰን፤ ዮሴፍ አቬኖል የዋና ጸሐፊነት ተግባሩን በትክክል እንዲፈጽም አስገደዱት። የፈረንሣይ መንግሥት መሪ ፒየር ላቫልም ጠቅላላው ጉባኤ በጣልያን ላይ የኤኮኖሚ እገዳ ከማድረግ እንዲዘገይ ያቀደውን ሐሳብ የሚደግፍለት በማጣት ብቻውን ስለሆነ፤ ትልቅ ጉድ ፈላበት። በግፈኛው ወራሪ መንግሥት ላይ እርምጃ እንዲወሰድ ቆርጠው ከተነሡት ከሃምሳዎቹ መንግሥታት መካከል ፈረንሣይ ለብቻዋ ተለይታ ለሙሶሊኒ መቆም ስለማትችል፤ የኤኮኖሚው እገዳ እንዲደረግ ድምጺን መስጠት ግዴታ ሆነባት። ላቫል ይህን እርምጃ የወሰደው፤ ተቸግሮና መውጫ መንገድ አጥቶ መሆኑን ሙሶሊኒ አልተረዳለትም። በገኔቭ ለሚገኘው እንደራሴው ለባሮን አሉይዚ፤ በየሰዓቱ በሚያስተላልፍለት ቴሌግራም፤ በኤኮኖሚው እገዳ ጉዳይ ላቫል ምን ያህል እንደረዳን በአስቸኳይ ግለጽልኝ እያለ ነው። ባሮን አሉይዚ፤ ላቫል የገጠመውን ችግር ደህና አድርጐ ስለሚያውቅ፤ በተቻለ መጠን ክቡር ዱቼ ፕሮብሌሙን ተረድቶ እንዲታገሰው ልመና አቅርቧል።

« ... አንቶኒ ኤደንና ረዳቶቹ፤ የፈረንሣይ ጠቅላይና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ለፋሽስት መንግሥት ዋና አገልጋይ ሆኗል በማለት በገኔቭ በሹክሹክታ የሚያሰራጩትን ዜና የብዙ አገሮች መልዕክተኞች እየተከተሉ፤ በፒየር ላቫል ላይ የማሾፍና የንቀት መንፈስ ያሳዩታል። ይሁን እንጂ፤ ወዳጃችን ላቫል እኛን ለመርዳት ውስጥ ውስጡን መታገሉን አላቋረጠም።

እርግጥ ነው ! ክቡር ዱቼ ኢትዮጵያ በፈጠረችው ችግር ምክንያት የጦር እርምጃ በመወሰዱ፤ ሊግ ኦፍ ኔሽን በፋሽስቱ መንግሥት ላይ የኢኮኖሚ እገዳ ማድረግ አይገባውም በማለት፤ በስብሰባው አዳራሽ በኦፊሲየል መናገር አልቻለም። እንደዚህ የተናገረ እንደሆነ፤ የፈረንሣይ ፓርላማ ወዲያውኑ ጠርቶ ከጠቅላይ ሚኒስትርነቱ እንደሚሽረው የታወቀ ነው። የላቫል መንግሥት ከወደቀ ደግሞ፤ ተተኪው ከራዲካሎቹና የኢትዮጵያ ደጋፊዎች ከሆኑት፤ ከነ ኤድዋርድ ሔሪዮ መካከል ስለሚሆን፤ ለእኛ ትልቅ ችግር ይፈጠርብናል።

... በመንግሥታችን ላይ ስለሚፈረደው የኢኮኖሚ እገዳ፤ ዝርዝሩን አጥንቶ እንዲያቀርብ የተሠየመው ኮሚቴ አሥራ ስምንት፤ ሥራውን በማፋጠን ላይ ነው። ይህ ኮሚቴ በሚያቀርበው ዝርዝር፤ እኛን በጣም የሚጐዱንን እንደ ነዳጅ ዘይት የመሳሰሉትን በመጀመሪያ ደረጃ ለማስቀረት፤ ላቫል ብዙ ጥረት በማድረግ ላይ ይገኛል። በግልጽ እንደምናየው ዋናው ተቀዋሚያችን አንቶኒ ኤደን ነው። ከመንግሥቱ ከተሰጠው መምሪያ እያለፈ የኢትዮጵያ ጠበቃ በመሆን በኢኮኖሚ እገዳ ጉሮሮአችንን ለማነቅ ይፈልጋል። ከዚህም በቀር ብዙዎች ወዳጆቻችን የነበሩትን አገሮች ሁሉ ያሳድምብናል። ለምሳሌም ያህል የሩማንያው ቲቱሌስኮ የከዳን፤ በኤደን ተንኮል መሆኑን እናምናለን። ... አሁን በአለንበት ሁኔታ የሚደረግብን የኢኮኖሚ እገዳ ዝርዝሩ ምን እንደሆነ ኮሚቴ አሥራ ስምንት እስኪያስታውቅ ድረስ የላቫል እርዳታ መጥቀም አለመጥቀሙን ማወቅ አንችልም። ስለዚህ፤ ይህን ሁሉ በመመዘን ለምንወስደው እርምጃ ጥቂት የትዕግሥት ዕድል እንዲሰጠው ክቡር ፈቃድዎን እለምናለሁ ... »

አሉይዚ፤ በማስታወሻው ላይ እንደገለጸው፤ ሙሶሊኒ ከገቤቭ እንደራሴው የቀረበለትን የዲፕሎማሲ ሐሳብ በሞቀ መንፈስ አልተቀበለውም። የሰጠውም መልስ የሚከተለው ነበር።

1. ጥር 7 ቀን 1935 ዓ.ም በጣልያንና በፈረንሣይ መካከል ሮም ላይ የተፈረመው ስምምነት በምሥጢር የሚጠበቅ መሆን የለበትም። ስለዚህ፤ ላቫል በስምምነታችን መሠረት በሊግ ኦፍ ኔሽን ሸንጐ ላይ እኛን ከመደገፍ የሚቆጠብ ከሆነ፤ ተገቢውን መልስ መስጠት ብቻ ሳይሆን፤ ተገቢውን እርምጃ እንድንወስድበት ያስፈልጋል።

2. ኤደን፤ ተቃዋሚያችን ሆኖ የሚፈጥርብን ችግር ሁሉ አንተ እንዳልከው በራሱ ሐሳብ እየተመራ ብቻ ሳይሆን፤ የመንግሥቱም ድጋፍ እንዳለው ደርሰንበታል። የታላቋ ብሪታንያም መንግሥት ለኢትዮጵያ ቀም ጣልያንን ማጥቃት የሚጠቅመው ከሆነ፤ እኛም አጸፋውን በሌላ መንገድ ለመመለስ በቅርቡ እንወስናለን።

3. ኮሚቴ አሥራ ስምንት፤ በሚያዘጋጀው ዝርዝር፤ የነዳጅ ዘይት እገዳ ካልተደረገብን፤ ሌሎቹን ጥቃቶች ለመቋቋም የሚያቅተን አይመስለኝም። እጅግ ከተቸገርን፤ አሁን በኢትዮጵያ ላይ በምናደርገው ዘመቻ፤ ከእንግዲህ ወዲህ መቀሌንና መሳውን ትግሬን በእጃችን ካደረግን በኋላ፤ ከንጉሡ ጋር አንድ ዓይነት የዕርቅ ድርድር ለመክፈት

እንፈቅድ ይሆናል። ሆኖም ለጊዜው የተቆረጠ ውሳኔ ስለአሳደረግን ጉዳዩ በምሥጢር ተይዞ መቆየት አለበት።

4. ለፒየር ላቫል የወዳጅነት ሰላምታዬን ካቀረብክ በኋላ፤ በቃል ኪዳን ስምምነታችን መሠረት፤ በኢትዮጵያ ጉዳይ የምታደርግልን እርዳታ ከጓዳ ውስጥ ወጥቶ ወደ ትልቁ አዳራሽ እንዲቀርብ አስፈላጊ ይሆናል በልልኝ። ... »

ፖምፔዎ አሎይዚ፤ ከታላቁ መሪው የተላከለትን መልስ በጥንቃቄ አጥንቶ በግል ማስታወሻው ላይ የሚከተለውን አስተያየት አስፍሯል።

1. በጣልያን ላይ የሚደረጉት የኢኮኖሚ ዕገዳዎች፤ የነዳጅ ዘይትንና እንዲሁም ለኢንዱስትሪዎቻችን ማምረቻ እጅግ ጠቃሚ የሚሆኑትን ጥሬ ዕቃዎች ሁሉ የሚጨምር ከሆነ፤ በኢትዮጵያ ላይ የተጀመረውን ጦርነት ማቆም ግዴታ እንደሚሆንበት ሙሶሊኒ በሚገባ ተረድቶታል። ስለዚህ፤ ይህ እንዳይደርስ ያለን ዕድል፤ ኮሚቴ አሥራ ስምንት የሚያዘጋጀው ሕግ እጅግ የጠነከረ እንዳይሆን ብርቱ ጥረት ማድረግ ነው።

2. ሙሶሊኒ ስለ ላቫል የተናገረው ትክክል ነው። ሮም ላይ የተደረገው ስምምነት በጣልያንና በፈረንሣይ መንግሥታት መካከል መሆኑ ቀርቶ፤ የሁለት ወዳጆች ሰዎች የምሥጢር ውል በማስመሰል ላቫል የሚሸፋፍነው ተገቢ አይደለም። ምንም እንኳ የፋሽስት ጦር ኢትዮጵያን መውጋቱን በይፋ መደገፍ ቢቸገርም፤ በጣልያን ላይ ከፍተኛ የኢኮኖሚ እገዳ እንዲወሰን እነ አንቶኒ ኤደን ለለአግባብ የሚያደርሱብንን ጉዳት በይፋ መቃወም ይገባው ነበር። ለዚህም የፈረንሣይ ዋና ዋና ጋዜጦች በሙሉ ዱቼን የሚደግፉ ስለሆኑ፤ ላቫልን የሚያስቸግረው ነገር አልነበረም።

## በጣልያን ላይ የሚወሰነው የኢኮኖሚ ዕገዳ

እ.ኤ.አ ጥቅምት 18 ቀን 1935 ዓ.ም ኮሚቴ አሥራ ስምንት በሕገ ወጡ የጣልያን መንግሥት ላይ የሚደረገው የኢኮኖሚ ዕገዳ ምንና ምን መሆናቸውን እንደሚከተለው ዘርዝሮ አቀረበ።

1. ወደ ጣልያን አገር የሚገቡት የጦር መሣሪያዎች በሙሉ እንዲታገዱ፤ ወደ ኢትዮጵያ የሚላኩት የመከላከያ የጦር መሣሪያዎች ግን ምንም ዓይነት እገዳ ሳይደረግባቸው በነፃ እንዲተላለፉ፤

2. ከሊግ ኦፍ ኔሽን አባል አገሮች፤ ለጣልያን መንግሥት ምንም ዓይነት የፊናንስ ብድር እንዳይሰጥና፤ የባንኮች ክሬዲትም የጣልያን ድርጅቶች ለሆኑትና ለግለሰቦችም ጭምር እንዲከለከሉ፤

3. የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል አገሮች ማናቸውንም የጣልያን የኢንዱስትሪ ምርቶች የሆኑትን ዕቃዎችና ሸቀጣ ሸቀጦች እንዳይገዙ፤

4. ለጣልያን ኢንዱስትሪዎችና ፋብሪካዎች ማምረቻ ጠቃሚ ናቸው የሚባሉት ጥሬ ዕቃዎች ሁሉ ለጣልያን እንዳይሸጡ፤

5. በዚህ በተወሰነው የኢኮኖሚ ዕገዳ ምክንያት አንዳንድ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል አገሮች የኢኮኖሚ እንቅስቃሴያቸው ችግር ላይ እንዳይወድቅባቸው ሊጉ ድጋፍ እንዲሰጣቸው፤

ከዚህ በላይ እንደሚታየው የኢኮኖሚ እገዳ እንዲደረግ በተወሰነው ዝርዝር ውስጥ፤ በተለይ የነዳጅ ዘይት ጉዳይ አለመጨመሩ ለዱቼ ሙሶሊኒ ትልቅ ደስታ ሆኗል። የኮሚቴ አሥራ ስምንት አባሎችን ማርከ፤ እነ አንቶኒ ኤደን ያደረጉትን ጥረት በማክሸፍ፤ በኢኮኖሚ እገዳ ዝርዝር ውስጥ ለጊዜው የነዳጅ ዘይት እንዳይጠቀስ ያስደረገው፤ የዱቼ ዋና ወዳጅና የፈረንሣይ ጠቅላይና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ፒየር ላቫል ነው። በዝኔቭ የሙሶሊኒ እንደራሴ የሆነው ባሮን አሉይዚ ለጌታው በላከው ራፖር፤ የላቫል እርዳታ ምን ያህል እንደጠቀመ ዘርዝሮ አስረድቷል። ከዚህ በኋላ ደካክሞ የነበረው የሙሶሊኒ ሞራል እየነቃ ስለመጣ፤ የሊግ ኦፍ ኔሽን አባላት በሆኑት የመንግሥታት መሪዎች ዘንድ፤ ከማንዳቶሬ ዱቼ ከፍ ያለ የዲፕሎማቲክ እንቅስቃሴ አደረገ። የዚህም ግቡ በእንግሊዝ መንግሥት ቆስቋሽነት፤ በጣልያን ሕዝብ ላይ ከፍተኛ አደጋ ለማድረስ በሊግ ኦፍ ኔሽን የተወሰነው የኢኮኖሚ እገዳ ምን ያህል ከሕግ ውጭ መሆኑን ለማስረዳት ነበር።

« ... የዛሬ ዐርባ ዓመታት የደረሰብን ታሪክ እንደሚያሳየን፤ "ምኒልክ" የተባለው የኢትዮጵያ ንጉሥ፤ የጣልያን መንግሥት ያልተዘጋጀበትን ጊዜ ጠብቆ፤ በኤርትራ ግዛታችን ወሰን አካባቢ በከፈተብን ጦርነት በብዙ ሺህ የሚቆጠሩ ዜጎቻችን ካለቁ በኋላ፤ ኢትዮጵያ የነጭ ዘር በሆነ ሕዝብ ላይ ድልን ተጎናጸፈች እየተባለ እስከ ዛሬ ሲነገር ይኖራል። ዛሬ ደግሞ ንጉሥ ኃይለሥላሴ፤ ከዚህ ቀደም የደረሰውን የምኒልክን ምሳሌ በመከተል፤ የኤርትራ ግዛታችንን እነጥቃለሁ ብሎ በብዙ መቶ ሺህ የሚቆጠር ጦር አዘጋጅቶ ሊወጋን መምጣቱን በይፋ አስታወቀን። ንጉሥ ኃይለሥላሴ እኛን ለመውጋት በመዘጋጀት ላይ መሆኑን ቀደም ሲል በመስከረም 25 ቀን 1935 ዓ.ም ለሊግ ኦፍ ኔሽንም አስታውቆ ነበር። በዚህ ጊዜ እኛም ሳይቀድመን መቅደም አለብን በማለት የመከላከያ ጦርነት በመጀመራችን፤ ሊግ ኦፍ ኔሽን ከዚህ ቀደም በማንም አገር ላይ ያልደረሰ ከባድ የኢኮኖሚ ቅጣት አወጀብን። በሊግ ኦፍ ኔሽን ዳኝነት የጣልያን ኃጢያቷ፤ ጠላቷ ተዘጋጅቶ ሊወጋት ሲመጣባት፤ የቤቷን በር ሰብሮ እስኪገባ ድረስ በመጠበቅ ፋንታ፤ ከአጥር ውጭ ወጥታ መከላከያዋን ለምን ተጠቀመች ? ተብሎ ነው። እንግዲህ ! ይህ ዓይነቱ ፍርድ በምን ላይ የተመሠረተ ነው ? ይህን የመሰለውስ ፍርድ ከዚህ ቀደም ደርሶ ያውቃል ወይ ? ... ደርሶ የታየ ከሆነም ከነማስረጃው ለምን አይቀርብም ? ደግሞስ ዐርባ አራት ሚሊዮን የሆነውን የጣልያንን ሕዝብ፤ ከዓለም ጋር ተሳስሮ የሚያከናውነውን የኢኮኖሚ ሕይወት በአንድ ጊዜ ዘግቶ አደጋ ላይ እንዲወድቅ ማድረግ ተገቢ ይሆናል ወይ ? ... ይህስ አድራጐት ለዓለም ሰላምና ለሕዝቦች ደህንነት የሚታሰበውን ሁሉ የሚያደፈርስና ወደ ከፋ

አቅጣጫ የሚመራ ሊሆን አይችልም ወይ ? ... ስለዚህ፤ የመንግሥታት መሪዎች በጣልያን ሕዝብ ላይ የወደቀውን፤ ይህን የመሰለውን ከሕግ ውጭ የሆነ ፍርድ አይተው፤ ተገቢውን ውሳኔ እንዲሰጡ በተስፋ እንጠብቃለን ... »

ከዚህ በላይ እንደሚታየው፤ በቅጥፈትና በፈጠራ ታሪክ ተዘጋጅቶ የቀረበላቸውን የፋሽስት ዲፕሎማሲ፤ ምንም እንኳ ብዙዎቹ የመንግሥታት መሪዎች ያልተቀበሉት ቢሆንም፤ አንዳንዶቹን ለመማረክ ወይም ለማታለል የሚረዳ ሳይሆን አልቀረም። ባሮን አሎይዚ፤ በማስታወሻው ላይ እንደገለጸው፤ ሊግ ኦፍ ኔሽን ለኢትዮጵያ በመፍረድ በጣልያን ላይ ይህን ያህል የኢኮኖሚ እገዳ ይወስናል ብሎ፤ ቤኒቶ ሙሶሊኒ አልጠበቀም ነበር። በዚህ ሲበሳጭና በኮሚቴ አሥራ ስምንት ላይ ተቃውሞውን ሲያጠነክር፤ ከዚህ የባሰ ችግር እንዲደርስበት ሌላ ቅጣት ተጠንስሶ መጣበት።

ኅዳር 10 ቀን 1935 ዓ.ም በካናዳ መንግሥት መልዕክተኛ በዶክተር ሪዴል እና (Dr. Riddell) በእንግሊዙ በአንቶኒ ኤደን አማካይነት፤ ከዚህ ቀደም በዝርዝሩ ውስጥ ያልገቡት፤ የነዳጅ ዘይት፤ የከሰልና የብረታ ብረት እገዳዎች እንዲደረጉ፤ ጥያቄው ለኮሚቴ አሥራ ስምንት ቀረበ። ሙሶሊኒ ይህንን ሲሰማ በጣም ስለደነገጠ፤ ከኢትዮጵያ ጋር ዕርቅ ለመደራደር የሚቻልበትን መንገድ ማጥናት ጀምሮ ነበር። ከአሎይዚ ማስታወሻ ላይ እንደተገኘው፤* ሙሶሊኒ ስለ ዕርቁ ጉዳይ ፍላጎቱን ያመለከተው፤ « ከኢትዮጵያ፣ በሰሜን በኩል የትግራይን አውራጃ በሙሉ ከኤርትራ ጋር ለማቀላቀልና፤ በደቡብ በኩል ደግሞ ኦጋዴንን ከሱማሌ ጋራ ለማዋሀድ፤ ንጉሡ ከተስማሙ እንቀበላለን » የሚል ነበር።

ሙሶሊኒ በዚህ ዓላማ ፀንቶ ጉዳዩን ለአስታራቂዎች ከማስተላለፉ በፊት፤ በድንገት ሳያስበው መጀመሪያ ከጃፓን፤ ቀጥሎ ከአሜሪካ፤ እጅግ አስደሳች የሆኑ ዜናዎች ስለደረሱለት፤ ወዲያውኑ ሐሳቡን በመለወጥ የሰላሙን ጉዳና ከመከተል ይልቅ፤ የተጀመረውን ጦርነት መቀጠል ያዋጣኛል ብሎ ወሰነ።

የጃፓን ንጉሠ ነገሥት መንግሥት፤ ጥቅምት 18 ቀን 1935 ዓ.ም ሊግ ኦፍ ኔሽን በጣልያን ላይ የመጀመሪያው ክፍል የኢኮኖሚ እገዳ እንዲደረግ ሲወስን፤ የድጋፍ ድምፅ ሰጥቶ እንደነበረ ይታወሳል። አሁን ደግሞ፤ በሁለተኛው ዙር እንደ ነዳጅ ዘይት የመሳሰሉትን ለማገድ፤ እነ አንቶኒ ኤደን በሚሰናዱበት ጊዜ፤ በሮም ያለው የጃፓን አምባሳደር ሙሶሊኒ ቢሮ ሔዶ፤ የቶኪዮ መንግሥት ለጣልያን ቤንዚን ለመሸጥ ፈቃደኛ መሆኑን በማስታወቅ፤ ለፋሽስቱ መሪ ያልጠበቀው ከፍ ያለ እርዳታ አበረከተለት። ዱቼም ወዲያውኑ ለእንደራሴው ለአሎይዚ ስልክ ደውሎ፤ « ... ወደ አፍሪካ ላሰማራነው ጦራችን፤ የጃፓን መንግሥት የሚያስፈልገንን ቤንዚን ሊሸጥልን ስለተስማማ ችግራችን ተወግዶልናል። ለእኛ ለሮም ኑሮአችን ግን፤ ሌላ ይህን የመሰለ ዕድል እስከሚገጥመን በእግር መኪተን ይኖርብናል ... » አለው። ዲክታተሩ፤ ይህን ደስታና ፌዝ የተቀላቀለበት ቃል በተናገረ ዐርባ ስምንት ሰዓት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ ደግሞ፤ ሌላ ተጨማሪ አዲስ ነገር ብቅ አለለት።

ዩናይትድ ስቴትስ ኦፍ አሜሪካ፤ ምንም እንኳ ለጣልያንም ሆነ ለኢትዮጵያ የጦር መሣሪያዎች መሸጤን አቆማለሁ ብሎ ያደረገው ውሳኔ

---

* Baron Aloisi Journal 1935

እንደተጠበቀ ቢሆንም፤ ለሙሶሊኒ መንግሥት እስከ ዛሬ የሚሸጠውን የነዳጅ ዘይት ወደፊትም የሚቀጥል መሆኑን፤ ከዋሽንግተን ስቴት ዲፓርትመንት አስታወቀ። በዚህ አኳኋን፤ እነ አንቶኒ ኤደን የነዳጅ ዘይት እገዳ እንዲደረግ የሚያደርጉት ጥረት የሚሳካ ቢሆን እንኳ፤ የአሜሪካ ውሳኔ ለሙሶሊኒ ትልቅ ድጋፍ ይሆንለታል ማለት ነው። እስከ ዛሬም ድረስ፤ ሊግ ኦፍ ኔሽን የነዳጅ ዘይት እገዳ ባለማድረጉ፤ የፋሽስቱ መንግሥት ቀድሞ ባለው ኮንትራት መሠረት ከሩሲያና ከሩማንያ፤ እንዲሁም ከአሜሪካና ከቬንዙዌላ ግዥውን እያፋጠነ፤ ሪዘርቩን ከፍ ማድረጉ አልቀረም ነበር። አሁን ደግሞ ከጃፓንና ከአሜሪካ የተገኘው ተስፋ ትልቅ ስለሆነ፤ የሙሶሊኒን ዕብሪትና ፉከራ የሚያፋፍመው እንጂ የሚገታው አልሆነም።

ቤኒቶ፤ አምሊካር፤ አንድሬአ ሙሶሊኒ ሲጨነቅበት የከረመው የነዳጅ ዘይት ጉዳይ፤ ጥሩ መፍትሔ የተገኘለት መሆኑን ሲያውቅ፤ በመላ ጣልያን በሰሜን ሆነ በደቡብ፤ በምሥራቅ ሆነ በምዕራብ፤ በደመቀ አጀብ እየተዘዋወረ በዚያ በታወቀው የፕሮፓጋንዳ ዲስኩሩ ሕዝቡን ለመማረክና "አንተ እንዳልክ " ብሉ እንዲሰለፍለት እርምጃ ወሰደ።

« ... የጣልያን ሕዝብ ስማ ! ለታሪክህ ክብርን፤ ለሕይወትህ ብልጽግናን ለማግኘት እንድትችል አስበን የጀመርነውን ጉዞ አናቋርጥም። ከግባችንም ሳንደርስ አንቆምም። ከአገራችን አራት ጊዜ እጥፍ የሆነ ስፋት ያላት፤ ኢትዮጵያ የተባለችው በጭለማው ዓለም ውስጥ የምትገኝ የፌምዳሎች መከማቻ አገር፤ በቅርቡ የጣልያን ግዛት ትሆናለች። እንደምታውቁት "አድዋ " በእጃችን ሆኖ ባንዲራችን ይውለበለብበታል። ነገም በሌሎቹ የኢትዮጵያ አውራጃዎች ሁሉ፤ ጀግናው የጣልያን ሠራዊት ድል እየመታ ይገዝበታል። ... በዓለም ላይ የኢኮኖሚ እገዳ በማሳወጅ፤ አደጋ ላይ ሊጥሉን ታጥቀው የተነሡብን የታላቋ ብሪታንያና የአንዳንድ ተቀዋሚዎቻችን መንግሥታት፤ እስካሁን የተመኙትን ለማየት አልቻሉም። ወደፊትም ለማየት አይችሉም። የጣልያን ሕዝብ ብርቱ ነው ! የጣልያን ሕዝብ ቆራጥ ነው ! የጣልያን ሕዝብ ጀግና ነው ! እንኳን ለችግር ለጦር ይመከታል። ... በዚህ በታወቀው ዝናችን የሚቀኑብንና የሚጠሉን ጥቂቶች አገሮች ቢኖሩም፤ የሚያደንቁንና የሚፈሩን ብዙዎች ናቸው።

በእንግሊዞች አነሣሽነት በሊግ ኦፍ ኔሽን ፍርደ ገምድል ውሳኔ መሠረት፤ ጣልያን የምታመርታቸውን የኢንዱስትሪ ውጤቶች ሁሉ አንገዛም ያሉትና፤ ጣልያንም በበኩሏ የሚያስፈልጓትን ጥሬ ዕቃዎች አንሸጥላትም ብለው ገበያቸውን የዘጉባት አገሮች ሁሉ፤ በዚህ ውሳኔ ለምን ያህል ጊዜ መቀጠል እንደሚችሉ አይታወቅም። በእኛ አስተያየት እንኳንስ ለብዙ ወራት፤ ለጥቂት ሳምንታትም ቢሆን ችግሩን መቋቋም እንደማይችሉ ገምተናል። እነዚህ ታናናሽ መንግሥታት ሁሉ፤ ምንም እንኳ ሊግ ኦፍ ኔሽን አለአግባብ በእኛ ላይ የወሰደውን እርምጃ ለመቃወም፤ በእንግሊዞች ተፅዕኖ ምክንያት ባይቻላቸውም፤ ከፋሽስት መንግሥት ጋር ያላቸውን የኢኮኖሚና የንግድ ግንኙነቶች ለማቋረጥ ጨርሶ እንደማይፈልጉ እናውቅ ነበር። በዚህም መሠረት፤ እነዚህ አገሮች፤ እስከዛሬ ድረስ ለጣልያን የሚሸጧቸውንና ከጣልያንም የሚገዟቸውን ዕቃዎች ያለ ችግር ለመለዋወጥ እንዲቻል፤ አንድ የሊግ ኦፍ ኔሽንን ሕግ የማይከተል አገር ፈልጉና አዘጋጁልን ብለው ስለጠየቁን፤ እኛም ወዳጃችን ከሆነ ከአንድ

መንግሥት ጋር ተነጋግረን፤ በእሱ በኩል ማናቸውንም የንግድ ዕቃዎች እንዲያስተላልፍልን አድርገናል።*

በዚህ ዘዴ አንዳንድ ችግሮቻችንን ለማስወገድ ብንችልም፤ ባላጋራችን የሆነው የእንግሊዝ መንግሥት አልተኛልንም። ... የልማት እንቅስቃሴያችን ሞተር የሆነውን የነዳጅ ዘይትና ሌሎቹንም ለኢንዱስትሪዎቻችን ምርት እጅግ አስፈላጊ የሆኑትን፤ እንደ ጥጥ፣ እንደ ከሰልና ብረታ ብረት የመሳሰሉትን ሁሉ ለመግዛት እንዳንችል፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን የማገጃ ሕግ እንዲወጣብን ከእንግሊዝና ከካናዳ መንግሥታት ተጠይቋል። በእንግሊዞችና በወዳጆቻቸው አስተያየት፤ ሊግ ኦፍ ኔሽን ይህንን ሁለተኛውን እርምጃ ሲወስድብን፤ በጥቂት ቀናት ውስጥ ፍርስርሳችን ወጥቶ ትልቅ አደጋ ላይ ወድቀን ለማየት ይጠባበቃሉ። ይህ ከንቱ ምኞት ነው። ባላጋራዎቻችን የሚመኙልንንና የሚጠብቁትን ለማየት ዕድል እንደማይገጥማቸው አረጋግጥላችኋለሁ።

ሊግ ኦፍ ኔሽን በሁለተኛ ደረጃ ሊያደርግብን ይዘጋጃል እየተባለ የሚወራው የነዳጅ ዘይት እገዳ ገና በኮሚቴ ተጠንቶ ከመወሰኑ በፊት፤ የዩናይትድ ስቴትስ ኦፍ አሜሪካና የጃፓን መንግሥታት፤ የጣልያን ሕዝብ አለአግባብ ችግር ላይ መውደቅ የለበትም ብለው በማሰብ፤ ከነዳጅ ዘይት ምርታቸው ሊያካፍሉን ፈቃደኛነታቸውን ገልጸውልናል። ለእነዚህ አገሮች የጣልያን ሕዝብ ውለታቸውን ምንጊዜም አይረሳውም። ሌሎቹም እስከዛሬ ድረስ ነዳጅ ዘይት ሲሸጡልንና ከእኛም የኢንዱስትሪ ምርቶቻችንን ሲገዙ የቆዩት አገሮች፤ ምንም እንኳ በሊግ ኦፍ ኔሽን አዳራሽ ከእንግሊዞች ጋር ቆመው ለይምሰል እኛን እያወገዙ ሲደንሱ ቢታዩም፤ በጀርባ ከእኛ ጋር ያላቸውን ገበያ የሚያቋርጡ አለመሆናቸውን አረጋግጠውልናል። ስለዚህ፤ የጣልያን ሕዝብ በርታ ! ተስፋህን አጠንክር ! በጀመርነው ጉዞ ድልን እየተጐናጸፍን መላ ኢትዮጵያን ግዛታችን እናደርጋታለን። ባላጋራዎቻችን ሆነው የሚያስቸግሩንን እንግሊዞችንና ሌሎቹንም ጥቂቶቹን ተከታዮቻቸውን እቦታቸው እንመልሳቸዋለን ... »

ከዚህ በላይ እንደታየው፤ ቤኒቶ ሙሶሊኒ በመላ ጣልያን ዋና ዋና ከተሞች እየተዘዋወረ ያደረጋቸውን የፕሮፓጋንዳ ዲስኩሮች፤ ሕዝቡ ያለ አንዳች ቅሬታ ሙሉ ድጋፉን ያበረከተለት መሆኑን ብዙዎቹ የፖለቲካ ታዛቢዎች መስክረዋል። እርግጥ ነው! ሙሶሊኒ በኢትዮጵያ ላይ የሚያካሂደው ጦርነት ለጣልያን ሕዝብ ሕይወት ትልቅ ጸጋ ነው እያለ እንደዚያ ሲጮህ፤ የዓለም መንግሥታት ያወጡትን ሕግ የጣሰ ግፈኛ መሪ መሆኑን የሚነግረው አላገኘም። እንዲያውም ይግረማችሁ! ብሎ፤ ዲስኩሩን ወደ ቀድሞው የጣልያን ታሪክ በመመለስ፤ እነ ጁሴፔ ማዚኒ (Mazzini) ለአገር ፍቅር ያደረጉትን መሥዋዕትነት፤ እነ ጋሪባልዲ (Garibaldi) ለአገር አንድነት የፈጸሙትን ጀግንነት እየጠቀሰ፤ የራሱንም ታሪክ ከእነሱ ጋራ በ6ማዛመድ፤ ለጣልያን ትልቅነትና

ዕድገት የሠራቸውን ሁሉ እየዘረዘረ ከመፎከር አልተቆጠበም። በየከተማው አደባባይ እየተሰበሰበ ይህን የፕሮፓጋንዳ ዲስኩር እንዲያዳምጥ የታዘዘውም

---

* በሌላ አነጋገር ይህ ወዳጅ መንግሥት የጣልያንን ዕቃዎች እየተቀበለ ለፈላጊዎቹ የሚሸጥና፤ ጣልያንም የሚያስፈልጓትን ሁሉ ከየአገሩ እየገዛ ለጣልያን የሚያቀርብ ነው ማለት ነው።

ሕዝብ እጅግ በጋለ መንፈስና በጋለ ስሜት፤ ለዱቼ ንግግር ደስታውን ከመግለጽ በስተቀር ሌላ ምርጫ እንዳልነበረው ለማንም ግልጽ ነው።

እንግዲህ ! ዲክታተሩ በሁለት መንገድ ሞራሉን ለማጠናከር ችሏል።

1ኛ/ ሊግ ኦፍ ኔሽን በጣልያን ላይ የኤኮኖሚ እገዳ እንዲደረግ የወሰደውን እርምጃ፤ ሕዝቡ ለመቋቋም ዝግጁ መሆኑን ተስማምቶ ድጋፉን ገልጾለታል።

2ኛ/ ሊግ ኦፍ ኔሽን በተጨማሪ የነዳጅ ዘይትን ለማገድ የሚወስንበት ከሆነ፤ ከአሜሪካና ከጃፓን ከሚያገኘው እርዳታ በላይ፤ አንዳንዶቹም አገሮች ውስጥ ውስጡን መንገድ እየፈለጉ እንደሚሸጡለት ቃል ገብተውለታል።

3ኛ/ ሊግ ኦፍ ኔሽን በእነ አንቶኒ ኤደን የተጠየቀውን የነዳጅ ዘይት እገዳ ጉዳይ፤ እስከአሁን በኮሚቴ አሥራ ስምንት ንግግር እንዲጀመርበት አላደረገም። ይህም ጉዳይ እነ ፒየር ላቫል በሥልጣን እስከ ቆዩ ድረስ፤ ይህን የመሰለው ጣልያንን የሚጐዳ ነገር በቶሎ ይወሰናል ብሎ መጠበቅ አይቻልም። በዚህም አኳኋን፤ ዱቼ የሚገኝበት ሁኔታ በብዙ ረገድ የሚያደፋፍረው ስለሆነ፤ የጦርነቱን ሒደት በማፋጠን መላ ኢትዮጵያን በቶሎ መያዝና ከዚያም በኋላ፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን ላይ አይበገሬነቱን አሳምኖ፤ የሚፈልገውን ሁሉ ለማድረግ ከመመኘት በስተቀር፤ ሌላ ሰላማዊ የሆነ መንገድ የሚያስብ አልሆነም።

**Reference:** a/ societé de Nations Journal Officiel 1935-1936
b/ Baron Aloisi Journal 1935